ኵሉ ፡ ዘያረክብ ፡ እምሕሠማት ፡ እው ፡ ሞተት፡ ይደልዎ ፡ ሰዳ ። ወእመኒ ፡ ኢዐደወ ፡ ወኮነ ፡ ዘረከባ ፡ በሀኬተ ፡ ዚአሁ ፡ እው ፡ በመግቦቱ ፡ ይደልዎ ፡ ሰዳ ። ወእመሰ ፡ ኢኮነ ፡ ከማሁ ፡ እው ሀሰወ ፡ እግዚአ ፡ ምስሌሁ ፡ ኢይደልዎ ፡ ሰዳ ። ወለእመ ፡ ኮነት ፡ በሀሰብ ፡ ወጠፍአት ፡ ይከውን ፡ ጥፍአታ ፡ በዓሰበ ፡ ዚአሃ ። ወለእመ ፡ ተዐደወ ፡ እመካን ፡ ዘተወሰነ ፡ የሀብ ፡ ለእውሓሲ ፡ ተውሳከ ፡ ዓሰቡ ፡ በዘተዐደወ ።

፩ሺ.፰ ወኵሉ ፡ ዘይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይሥራዕ ፡ ቦቱ ፡ ውስተ ፡ ንዋዩ ፡ ይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ያውሕስ ፡ ኵሎ ፡ ንዋዮ ፡ ዘይሠርዕ ፡ ቦቱ ፡ ከመ ፡ ያውሕስ ፡ ኵሎ ፡ ዘይከውኖ ፡ ለበቍዔት ፡ በዓሰቡ ፡ ምስለ ፡ ዳኅናሁ ፡ ወሰቅበቱ ፡ ርእሱ ። ወይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይንሣእ ፡ ሤጠ ፡ ዚአሁ ፡ ለዘጠፍአ ፡ እምኔሁ ፡ በሰለተ ፡ ጥፍአቱ ፡ ለእመ ፡ ተዐደወ ፡ ላዕሌሁ ፡ ውስቱ ። እመ ፡ ኮነ ፡ እምእንስሳ ፡ ውእቱ ፡ ወሞተ ፡ እው ፡ ጐየ፡ ኢይረክቦ ፡ ሰዳ ፡ ዘእንበለ ፡ ዳእሙ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘወሀበ ፡ ተሐባዬ ፡ ለእግብእቱ ፡ ድኅነ በኵሉ ። ወለእመ ፡ ተግእዘ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለየውሓሲ ፡ ምስለ ፡ መሐላው ። ወእመ ፡ እኮ ፡ ሠናይ ፡ ከመ ፡ ኢትትወሐስ ፡ ሕሰተ ፡ ወኢተእኅዝ ፡ እኅዘ ፡ ወኢትትሀሰብ ፡ ዘእንበለ ፡ በትእዛዘ ፡ እውሓሲ ፡ በዕድሜ ፡ ዘተወሰነ ።

ስለ ፡ አደራ ፡

ኛት ፡ ሁሉ ፡ ወይም ፡ ብትሞት ፡ ሰዳ ፡ (መክፈል) ፡ ይገባዋል ። ባያልፍ ፡ ጉዳት ፡ ያገኛትም ፡ በሰንፍናው ፡ ወይም ፡ ባመጋገቡ ፡ ቢሆን ፡ ሰዳ ፡ ይገባዋል ። እንዲህ ፡ ባይሆን ፡ ግን ፡ ወይም ፡ ጌታዋ ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ ቢኖር ፡ ሰዳ ፡ አይገባውም ። በክራይ ፡ ቢሆን ፡ ብትጠፋ ፡ ጥፋቷ ፡ በዋጋዋ ፡ ይሆናል ። ከተወሰነ ፡ ቦታ ፡ ቢያልፍ፡ በተሳለፈበት ፡ የኪራዩን ፡ ጭማሪ ፡ ለአዋሰው ፡ ይስጥ ።

፩ሺ.፰ በገንዘቡ ይሠራበት ዘንድ የሚገባው ሰው ፡ ሁሉ ፡ ያውስ ፡ ዘንድ ፡ የሚያዝዝበት ፡ ገንዘቡን ሁሉ ፡ ከዓይነቱና ፡ ራሱ ፡ ከመጠበቅ ፡ ጋር ፡ በኪራዩ ፡ ለጥቅም ፡ የሚሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ሊያሲዝ ፡ ይገባዋል ። ከተወሰነው ፡ በላይ ፡ ጨምሮ፡ ቢተላለፍ ፡ በጠፋበት ፡ ቀን ፡ የጠፋውን ፡ ዋጋ ፡ ከእርሱ ፡ ሊቀበል ፡ ይገባዋል ። ከእንስሳ ፡ ወገን ፡ ቢሆን ፡ ቢሞት ፡ ወይም ፡ ቢጠፋ ፡ ሰዳ ፡ አያገኘውም ። በሁሉ ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ ለመመለስ ፡ ዋስ ፡ የጠራ ፡ ቢሆን ፡ ነው ፡ እንጂ፡ ቢከራከሩ ፡ ከመሐላው ፡ ጋራ ፡ እንደአዋሹ ፡ ቃል ፡ ይሁን ። ያም ፡ ባይሆን ፡ በተወሰነ ፡ ቀን ፡ ያለአዋሹ ፡ ትእዛዝ ፡ ትውስት ፡ ባትዋስ ፡ መያዣ ፡ ባትይዝ ፡ ባትከራይ ፡ መልካም ፡ ነው ።

፩ሺ.፰፩ ወለእውሓሲ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ያግብእ ፡ ንዋዮ ፡ ጊዜ ፡ ፈቀደ ፡ ዘእንበለ ፡ ይኩን ፡ ዘቀደመ ፡ ወሰኖ ፡ እው ፡ ዘተሠርዐ ፡ ጊዜሁ ፡ እው ፡ ኢተፈጸመት ፡ ንሥእ ፡ በቍዔት ፡ ቦቱ ። ወኢትትዐቀብ ፡ ዓይኑ ፡ ምስለ ፡ በቍዔታት ፡ ዘቦቱ ፡ ዘከመ ፡ ዲናራት ፡ ወጠፋልሐ ፡ ብሩር ፡ ወዘይሰፈር ፡ ወይትሜዘን ፡ ሊቃሕ ፡ ውእቱ ፡ ወእኮ ፡ ሕሰት ።

፩ሺ.፰፩ ለሚያውስ ፡ ሰው ፡ የቀደመው ፡ ውሳኔ ፡ ወይም ፡ የተወሰነ ፡ ጊዜ ፡ ሳይደርስ ፡ ወይም ፡ በእርሱ ፡ ጥቅምን ፡ ማግኘቱ ፡ ካልተፈጸመች ፡ በወደደው ፡ ጊዜ ፡ ገንዘቡን ፡ ሊመልስ ፡ ይገባዋል ። ዓይነቱም ፡ በእርሷ ፡ ከሚገኙ ፡ ጥቅሞች ፡ ጋር፡ አትጠባበቅ ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ ዲናር ፡ እንደ ተመዘነ ፡ ብር ፡ እንደሚሰፈር ፡ እንደሚመዘን ፡ ያለ ፡ ብድር ፡ ነው ። ትውስት ፡ ግን ፡ አይደለም ።

# አንቀጽ ፳ወ፱ቱ ።

## በእንተ ፡ ማኅፀንት ።

፩ሺ.፰፪ ጠስ ፡ ፲ወ፳ቱ ፡ ወኵሉ ፡ ዘተወሰከ ፡ ላዕሌሁ ። ማኅፀንትሰ ፡ ንዋይ ፡ ይእቲ ፡ ዘይሁብ ፡ እግዓዚ ፡ ለዘያማኅፅኖ ፡ ከመ ፡ ይዕቀብ ፡ ሎቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ካዕበት ፡ እምኔሁ ፡ ጊዜ ፡ አግብእቶ ።

# አንቀጽ ፡ ፳፱ ።

## ስለ ፡ አደራ ፡ ይናገራል ።

፩ሺ.፰፪ ጠስ ፡ ፲ወ፳ ። ሁሉም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የተጨመረ ነው ። አደራስ ፡ ከእርሱ ፡ በሚመልሳት ፡ ጊዜ ፡ ያለትርፍ ፡ ይጠብቅለት ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ ባይ ፡ ለአደራ ፡ ተቀባይ ፡ የሚሰጣት ፡ ገንዘብ ፡ ናት ።

ወይእቲኒ ፡ እምነት ፡ ዘአማኅፀኒሃ ፡ ዘያነብራ ፡
ኀበ ፡ ዘያማኅፅኖ ። ወለዘሂ ፡ ተመክፈ ፡ ይደልዎ፡
ከመ ፡ ይሰቀብ ፡ በዐቢይ ፡ ጻሕቅ ፡ ወይኩን ፡ በቀ
በ፡ቱ ፡ ኪያሃ ፡ ከመ ፡ ንዋዩ ። ወለእመ ፡ ጠፍእት ፡
እምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ እልቦቱ ፡ ዕዳ ። ወለእመ ፡
ፈቀደ ፡ እግብእታ ፡ ለእግዚእ ፡ እንዘ ፡ ዳኅን ፡
ይእቲ ፡ በጊዜ ፡ ግብአታ ፡ ወአበየ ፡ ነሚአታ ፡
ይእቲ ፡ ጊዜ ፡ ለእመ ፡ ጠፍእት ፡ ወማስነት ፡
ማሰኖ ፡ ፍጥረታዊ ፡ ዘከመ ፡ እንስሳ ፡ መዋቲ ፡
እው ፡ ምንትኒ ፡ ዘያማስን ፡ በቍንቍኒ ፡ እው ፡
ተንሥአ ፡ ላዕሌሃ ፡ ዘኢይትከሀሎ ፡ ከመ ፡ ይሰ
ድዶ ፡ ዘከመ ፡ ውዕየት ፡ በእሳት ፡ እው ፡
ተሠጥመ ፡ እው ፡ ተበርብረ ፡ እው ፡ ሰረቅ ፡
እው ፡ ትሰግልት ፡ ኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይፍዲ ፡
ለእመ ፡ ኢተሀውቀ ፡ በስምዐ ፡ ጥዩቅ ፡ ከመ ፡
ኮነ ፡ ዝንቱ ፡ እምትሕሉቱ ፡ ወእከየ ፡ ምግ
ብናሁ ፡ ወኢዓቀቦቱ ፡ ላቲ ፡ ከመ ፡ ንዋዩ ፡
እሰመ ፡ ለዛቲ ፡ ግብር ፡ ይደሉ ፡ ተኀሥሦ ፡
በእንቲአሃ ፡ ወእመኒ ፡ ኮነ ፡ ዘአቅደመ ፡ ሠረዐ ፡
ውሳኔ ፡ በእንቲአሃ ፡ በተሰናእዎቶሙ ። ወለእመ
ኀሠሣ ፡ እግዚእ ፡ ወከልእ ፡ እምኔሁ ፡ ወው
እቱ ፡ እንዘ ፡ ይክል ፡ መጥዎታ ፡ ሎቱ ፡ እው ፡
ክሕደ ፡ ኪያሃ ፡ ወኀበአ ፡ እምነ ፡ ቦቱ ፡ ይፍዲ ፡
ኪያሃ ።

፩ሺ.፰፫ ወለእመኒ ፡ አስተዋዕአ ፡ በተለቅሖ ፡ ለነፍሱ ፡
እው ፡ ለካልኡ ፡ እው ፡ በተዓበየ ፡ ካልኣን ፡
እው ፡ በእኀዝ ፡ እው ፡ በውሕስት ፡ በሰሚተ ፡
ተወሐሰ ፡ እው ፡ ይትሐበይ ፡ ከመ ፡ ያግብእ ፡
ኪያሃ ፡ ኀበ ፡ ምዕቅብናሁ ፡ ለዘወሀቦ ፡ ኪያሃ ።
ወለእመሂ ፡ ወሀበ ፡ ማኅፀንተ ፡ ለካልኡ ፡ ዘእን
በለ ፡ እመክንዮ ፡ በሐዋረ ፡ ፍኖት ፡ እው ፡ በካ
ልእ ፡ ይትሐበይ ፡ ኪያሃ ፡ እስከ ፡ ያገብእ ። ወኢ
ይደልዎ ፡ ለዳግማዊ ፡ ከመ ፡ ይመጥዋ ፡ ለእግ
ዚእ ፡ ዘእንበለ ፡ በትእዛዙ ፡ ለአማኅፀኒሃ ፡ ሎቱ፡
ወበቃለ ፡ ዚአሁ ፡ ገጸ ፡ በገጽ ፡ እው ፡ በመልእ
ክቱ ፡ እመኒ ፡ በሐዋርያሁ ፡ እው ፡ በጽሒፈ ፡
መልእክት ፡ እምርት ፡ እንተ ፡ ትነግር ፡ ጥዩቀ ፡
ትእምርት ።

፩ሺ.፰፬ ወኢይደሉ ፡ ለዘአማኅፀኑ ፡ ኀቤሁ ፡ ከመ ፡ ይእ
በይ ፡ እመጽሐፍ ፡ ዘእመ ፡ ጎቢ ፡ በትንግር ፡ ከመ፡
ማኅፀንት ፡ ሀለወት ፡ ኀቤሁ ፡ ወኢብውሕ ፡



ይህችውም ፡ ካደራ ፡ ተቀባይ ፡ ዘንድ ፡ የሚያኖ
ራት ፡ ያደራ ፡ አስቀማጭ ፡ እምነት ፡ ናት ።
ለተቀበላትም ፡ ሰው ፡ በታላቅ ፡ ትጋት ፡ ሊጠ
ብቃት ፡ ይገባዋል ። እርሷን ፡ መጠበቁም ፡
እንደ ፡ ገንዘቡ ፡ ይሁን ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ብት
ጠፋ ፡ ዕዳ ፡ የለበትም ። በምትመለሰበት ፡ ጊዜ ፡
ደኅና ፡ ሳለች ፡ ለባለቤቷ ፡ ሊመልስለት ፡ ቢ
ወድ ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ መቀበሏን ፡ እንቢ ፡ ቢል ፡
ያንጊዜ ፡ ባሕርያዊ ፡ መጥፋትን ፡ ፈጽማ ፡ ብት
ጠፋ ፡ ይኸውም ፡ እንደሚች ፡ ከብት ፡ ወይም ፡
ነቀዝ ፡ እንደሚያበላሸው ፡ ማናቸውም ፡ ነገር ፡
ቢሆን ፡ ነው ። ወይም ፡ ሊከላከልለት ፡ የማይቻ
ለው ፡ ነገር ፡ በእርሷ ፡ ላይ ፡ ቢነሣ ፡ ይኸውም ፡
በእሳት ፡ እንደመቃጠል ፡ ወይም ፡ እንደመለ
ጠም ፡ ወይም ፡ እንደመዘረፍ ፡ ወይም ፡ እንደመ
ሰረቅ ፡ ወይም ፡ እንደመቀማት ፡ ቢሆን ፡ ይህ ፡
ከተንኮሉ ፡ ከመጋገቡ ፡ ከፋት ፡ እንደገንዘቡም፡
እድርጎ ፡ ካለመጠበቁ ፡ የተነሣ ፡ እንደሆነ ፡
በማስረጃ ፡ ምስክር ፡ ካልታወቀ ፡ ዕዳ ፡ መክ
ፈል ፡ አይገባውም ። ለዚች ፡ ሥራ ፡ ስለእርሷ ፡
መመራመር ፡ ይገባልና ። ስለእርሷ ፡ በመስማ
ማታቸው ፡ ውሳኔ ፡ መወሰንን ፡ ያስቀደመ ፡
ካልሆነ ፡ ጌታዋ ፡ ቢፈልጋትም ፡ ከእርሱ ፡ ቢከ
ለከለው ፡ ይኸውም ፡ ለእርሱ ፡ እርሷን ፡ መስ
ጠት ፡ ሲቻለው ፡ ወይም ፡ እርሷን ፡ ቢክድ ፡
መልሶም ፡ ቢያምን ፡ እርሷን ፡ ይክፈል ።

፩ሺ.፰፫ ለራሱ ፡ ወይም ፡ ለሌላው ፡ በመበደር ፡ ወይም ፡
ለሌሎች ፡ በማከራየት ፡ ወይም ፡ በማያገባ ፡
በተዋሰው ፡ ዋጋ ፡ በውስት ፡ ወይም ፡ እርሷን ፡
ወደሰጠው ፡ ሰው ፡ እደራነት ፡ እርሷን ፡ ሊመ
ልስ ፡ ይዋላት ፡ ዘንድ ፡ ቢያወጣጣት ፡ መን
ገድ ፡ በመሄድ ፡ ወይም ፡ በሌላ ፡ ሳያመካኝ ፡
ለሌላው ፡ አደራ ፡ ቢሰጣትም ፡ እርሷን ፡ እስኪ
መልስ ፡ ድረስ ፡ ዋስ ፡ ይጥራ ። ለሁለተኛውም ፡
ለእርሱ ፡ አደራ ፡ በሰጠው ፡ ሰው ፡ ትእዛዝና ፡
በቃሉ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ወይም ፡ በደብዳቤው ፡
በመልእክተኛውም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ የመልእ
ክቱን ፡ እርግጠኛነት ፡ የምትናገር ፡ የታወቀች ፡
ደብዳቤ ፡ በመጻፍ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ለጌታዋ ፡
ሊሰጥ ፡ አይገባውም ።

፩ሺ.፰፬ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ ለአስቀመጠበት ፡
ሰው ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ እንዳለች ፡
ከምትናገር ፡ ከአደራ ፡ አስጠባቂ ፡ ደብዳቤ ፡ የተ

ለዘ፡ይነብር ፡ ማኅፀንተ ፡ ኀቤሁ ፡ ከመ ፡ ይእበዩ፡ እጽሕፎቶ ፡ ማኅፀንት ፡ ዘይሁብዎ ፡ ዘትንግር ፡ ከመ ፡ ኀቢሁ ፡ ዘለወት ።

፩ሺ.፹፭ ወለእመ ፡ አዘዘ ፡ ወሃቢ ፡ ማኅፀንት ፡ ከመ ፡ ኢያውፅአ ፡ ወእውፅአ ፡ እው ፡ አዘዞ ፡ ከመ ፡ የሀባ ፡ ለእገሌ ፡ ወኢወሀባ ፡ ሎቱ ፡ እው ፡ አዘዞ ፡ ከመ ፡ ኢይመጥዋ ፡ ለካልእ ፡ ዘጥዩቅ ፡ ወመጠዋ ፡ ሎቱ ፡ እው ፡ አዘዞ ፡ ከመ ፡ ያንብራ ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ እሙር ፡ ወከመ ፡ ኢያንብራ ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ እገሌያዊ ፡ ወእበዩ ፡ ወኢኮነ ፡ እመንገለ ፡ ዓጸባ ፡ ዘከሠት ፡ ዘኢይትከሀሎ ፡ አንብሮታ ፡ ይትኣኀዝ ፡ በዕዳሃ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘወረሳ ፡ እምኀበ ፡ ዘነበረት ፡ ኀቤሁ ማኅፀንት ፡ ወእእመረ ፡ ባቲ ፡ ወተኀበሎ ፡ ከመ፡ ይገብራ ፡ ለእግዚእ ፡ ወኢገብራ ፡ ሎቱ ፡ ይትኣኀዝ ፡ በዕዳሃ ።

፩ሺ.፹፮ ወእመኒ ፡ ፈቀደ ፡ ነጊደ ፡ ርኁቀ ፡ ብሔረ ፡ ወኢረከበ ፡ ለእግዚእ ፡ ወኢለመጋቢሁ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ የሀባ ፡ ለፈታሒ ፡ ወእመ ፡ ኢተክህሎ ፡ ለብእሲ ፡ ምእመን ፡ ወለእመ ፡ ኢረከበ ፡ ለእግዚእ ፡ ማኅፀንት ፡ ይጽንሓ ፡ እስከ ፡ ሰደሚ ፡ መዋዕል ፡ ዘኢየሐዩ ፡ ከማሁ ፡ እምድኅሬሃ ። ወእምገ ፡ የሀባ ፡ ለወራስያኒሁ ፡ ወለእመ ፡ እልቦቱ ፡ ወራስያን ፡ ትእዛዝ ፡ ለመሥዋዕት ፡ ወያመጽእዋ ፡ በእንቲአሁ ፡ በዓሥራት ፡ ጽድቅ ። እመኒ ፡ በንሎቱ ፡ እው ፡ በመጽወት ፡ በእንቲአሁ ፡ በትእዛዘ ፡ ፈታሒ ፡ እው ፡ በሰማዕታት ።

፩ሺ.፹፯ ወይደልዎ ፡ ለእማኅፃኒ ፡ ወለዘእማኅፀኑ ፡ ኀቤሁ ፡ ሶሚረ ፡ ማኅፀንት ፡ ጊዜ ፡ ፈቀደ ፡ ኀበ ፡ ዘይትከሀሎ ፡ ለዘእማኅፀኑ ፡ ኀቤሁ ፡ ከመ ፡ የሀቦ ፡ ኪያሃ ፡ ወለእማኅፃኒ ፡ ከመ ፡ ይትመጠዋ ። ወለእመ ፡ እበየ ፡ ዘንተ ፡ ትከውን ፡ ዕዳ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወወፅአት ፡ ዕዳ ፡ እምተሐባዩ ፡ ካልእ ።

፩ሺ.፹፰ ወለዘሂ ፡ እስተጋብአ ፡ እማኅፀንት ፡ ለእስርሮ ፡ እው ፡ ዘይመስሎ ፡ ለዘንቱ ፡ ወፋትሖኒ ፡ ይትኮን ፡ ከመ ፡ ንዋይ ፡ ማኅፀንት ። ወለኮሰ ፡ ዘኮነ ፡ እማኅፀንት ፡ እምሳለ ፡ ዘይረብሕ ፡ እው ፡ ዘኮነ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ለዘንቱ ፡ ወፋትሖኒ ፡ ከመ ፡ ንዋይ ፡ ማኅፀንት ፡ በእንተዝ ፡ ፈታሒ ።

፩ሺ.፹፱ ወዘሂ ፡ ተወክፈ ፡ ማኅፀንተ ፡ በእግዚእ ፡ ወተመ



ነው ፡ እንቢ ፡ ሊል ፡ አይገባውም ። በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ ለሚያኖር ፡ ሰው ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ እንዳለች ፡ የምትናገር ፡ የሚሰጡትን ፡ አደራ ፡ ማስጻፍ ፡ እንቢ ፡ ሊል ፡ አይገባም ።

፩ሺ.፹፭ አደራ ፡ ሰጭ ፡ እንዳያወጣት ፡ ቢያዝዝ ፡ ቢያወጣት ፡ ወይም ፡ ለእገሌ ፡ እንዲሰጥ ፡ ቢያዝዘው ፡ ለእርሱም ፡ ባይሰጥ ፡ ወይም ፡ ለሌላ ፡ እንዳይሰጥ ፡ በእርግጥ ፡ ቢያዘው ፡ ለእርሱም ፡ ቢሰጣት ፡ ወይም ፡ ከታወቀ ፡ ቦታ ፡ ያኖራት ፡ ዘንድ ፡ እገሌ ፡ በሚባል ፡ ቦታ ፡ ውስጥ ፡ እንዳያስቀምጣት ፡ ቢያዝዘው ፡ እንቢም ፡ ቢለው ፡ እርሷን ፡ ማኖር ፡ ከማይቻለው ፡ ከተገለጠ ፡ ጭንቅ ወገን ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ በዕዳዋ ፡ ይያዛል ። አደራ ፡ ከተቀመጠችበት ፡ ሰው ፡ ዘንድ ፡ የወረሳት ፡ ቢሆን ፡ እርሷን ፡ ቢያውቅ፡ ለጌታዋ ፡ መንገር ፡ ሲቻለው ፡ ለእርሱ ፡ ባይነግረው ፡ በዕዳዋ ፡ ይያዛል ።

፩ሺ.፹፮ ወደሩቅ ፡ አገር ፡ ሊሄድ ፡ ወደዶ ፡ ጌታዋን ፡ ወይም ፡ አስተዳዳሪውን ፡ ባያገኘው ፡ ለዳኛ ፡ ሊሰጣት ፡ ይገባዋል ። ባይቻለውም ፡ ለታመነ ፡ ሰው ፡ ይስጥ ። ያደራውን ፡ ባለቤት ፡ ባያገኘው ፡ ከእርሷ ፡ በኋላ ፡ እንደርሱ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ እስከማይኖርበት ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ ይጠብቀው ። ከዚያ፡ በኋላ ፡ ለወራሾቹ ፡ ይስጣት ። ወራሾች ፡ ባይኖሩት ፡ ትእዛዝ ፡ ለመሥዋዕት ፡ ነው ። (ለመሥዋዕት ፡ ይታዘዝ) ፡ ስለእርሱ ፡ በጽድቅ ፡ መንገድ ፡ ይመጽወቷት ። በመኰለትም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በመመጽወት ፡ ስለእርሱ ፡ በዳኛ ፡ ትእዛዝ ፡ ወይም ፡ በምስክሮች ፡ ይሁን ።

፩ሺ.፹፯ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ ያስቀመጡበት ፡ ሰው ፡ በሚቻለው ፡ ግንዘብ ፡ እርሷን ፡ ይስጥ ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ አስቀማጭም ፡ ይቀበላት ፡ ዘንድ ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ ለአደራ ፡ አስቀማጭና ፡ እደራ ፡ ላስተመጡበትም ፡ ሰው ፡ አደራውን ፡ መሻር ፡ ይገባዋል ። ይህን ፡ እንቢ ፡ ቢል ፡ ዕዳ ፡ ትሆን በታለች ። ዕዳም ፡ ከሌላው ፡ ዋስ ፡ ወጣች ።

፩ሺ.፹፰ ለማረፍ ፡ ካደረው ፡ የሰበሰበት ፡ ወይም ፡ ይህን ፡ የሚመስለው ፡ ፍርዱ ፡ አደራን ፡ እንደ ፡ መቀበል ፡ ይሁን ። ከአደራ ፡ ወገን ፡ የሚረባ ውን ፡ የመሰለ ፡ ወይም ፡ የሆነው ፡ ይህንም ፡ የመሰለው ፡ ሁሉ ፡ ፍርዱም ፡ በዳኛ ፡ ቤት ፡ አደራ ፡ እንደማኖር ፡ ነው ።

፩ሺ.፹፱ አደራን ፡ ከጌታዋ ፡ የተቀበለ ፡ ሰው ፡ ከመል

ጠዋ ፡ እምእደ ፡ ሐዋርያው ፡ እግዚእ ፡ ውእቱ ፡ አማኅፃኒሁ ፡ ወሎቱ ፡ የሀበ ፡ ወአኮ ፡ ለሐዋርያው ፡ ዘእንበለ ፡ በትእዛዙ ፡ ወእመኒ ፡ ሞተ ፡ ትኩን ፡ ለወራሲዪሁ ። ወዘሂ ፡ ተወክፈ ፡ ማኅፀንተ ፡ እምዕዴ ፡ ወይቤሎ ፡ ከመ ፡ ይመይጣ ፡ ለካልኡ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይመይጣ ፡ ለዝኩ ፡ ካልእ ፡ ወያዐድዎ ፡ ከመ ፡ ይእቲ ፡ ማኅፀንት ፡ ወአኮ ፡ ከመ ፡ የሀባ ፡ ለአማኅፃኒሁ ፡ በእዴሁ ፡ ለካልኡ ።

፩ሺ፶ ወለእመ ፡ እንበሩ ፡ ፪ቱ ፡ ማኅፀንተ ፡ ኀበ ፡ ፩ዱ ፡ ኢይደልዎ ፡ መሀቢታ ፡ ለ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘእንበለ ፡ በሥምረተ ፡ ካልኡ ።

፩ሺ፶፩ ወለዘሂ ፡ ወሀብዎ ፡ ማኅፀንተ ፡ እመኒ ፡ ገብረ ፡ አው ፡ እንስሳ ፡ ወኢወሀቦሙ ፡ ሲሳየ ፡ ወኢስቴ ፡ እስከ ፡ ይመውቱ ፡ ይትኣኀዝ ፡ በሰዳሆሙ ። ወእመኒ ፡ ኮነ ፡ ይቤሎ ፡ ዘአማኅፀኖ ፡ ኢትሀቦሙ ፡ መብልዐ ፡ ወስቴ ፡ ወነሥኦ ፡ በዘሀበሙ ፡ እምኔሆሙ ፡ ለመፍቅዶሙ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይትኀሠሥ ፡ ኪያሁ ፡ እምበዓለ ፡ ማኅፀንት ። ወለእመ ፡ ካልእ ፡ ትከውን ፡ ኀቤሁ ፡ ከመ ፡ እንተ ፡ አኀዘ ፡ በእምኅን ፡ ዘወሀበ ፡ ወተወለደ ፡ እምተሐብዮቱ ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ወይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለዘወሀቦ ፡ ማኅፀንተ ፡ ምስለ ፡ መሐላሁ ። ወእምከመ ፡ ተኀጕለ ፡ በእንተ ፡ ማኅፀንት ፡ ወተፈድየ ፡ ሰዳ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ተአመነ ፡ በንዋዩ ፡ ወለእመ ፡ አምጽአ ፡ አማኅፃኒ ፡ ስምዐ ፡ ጥዩቀ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ።

፩ሺ፶፪ ወኢይደሉ ፡ ውሂበ ፡ ማኅፀንት ፡ ዘእንበለ ፡ ለዘ ፡ ያለምዶ ፡ ከዊነ ፡ እስተዋስኦ ፡ ወኅሢሦቱ ፡ በዓሉ ፡ ለተቀብሎቱ ፡ ንዋዩ ፡ እምድኅረ ፡ ለመደ ፡ እስተዋስኦ ፡ ወተወክፎ ።

፩ሺ፶፫ ወትበጽሕ ፡ ማኅፀንት ፡ በሞቱ ፡ ለዘእንበረ ፡ ኀቤሁ ፡ ወለዘአኀዞ ፡ ጋኔን ፡ እስከ ፡ ይሌቡ ።

፩ሺ፶፬ ወዘሂ ፡ ተወክፈ ፡ ማኅፀንተ ፡ ወእምዝ ፡ አእመረ ፡ ከመ ፡ አማኅፃኒሁ ፡ ሰረቃ ፡ አው ፡ ተዓገላ ፡ በኀይል ፡ ይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይትኤሎዋ ፡ በኅሰበት ። ወዘኢያስተሐመመ ፡ በንዋየ ፡ ማኅፀንት ፡ በከመ ፡ ያስተሐምም ፡ በንዋዩ ፡ ዓዲ ፡ ተንሕለ ፡ ወይትኀሠሥ ፡ አማኅፃኒ ፡ ከመ ፡ ኆሕላዊ ፡ ወጽንዑ ፡ ሕሊና ፡ ወተዐደዎ ፡ ዘእንበለ ፡ ይኩን ፡ በንእሰ ፡ ዓዲ ፡ ኮነት ፡ ላዕለ ፡ ንዋዩ ፡ ካልእት ፡ ግብር ።



እክተኛውም ፡ እጅ ፡ የወሰዳት ፡ ጌታዋ ፡ አደራ ፡ ባዩ ፡ ነው ። ለእርሱ ፡ ይሰጠው ፡ እንጂ ፡ እርሱ ፡ ካላዘዘ ፡ በቀር ፡ ለመልእክተኛው ፡ አይደለም ። ቢሞትም ፡ ለወራሾቹ ፡ ትሁን ። ከአንዱ ፡ አደራ ፡ የተቀበለ ፡ ለሌላም ፡ ስጥልኝ ፡ ቢለው ፡ ለዚያ ፡ ለሌላው ፡ ሊሰጣት ፡ ይገባዋል ። ይህችውም ፡ አደራ ፡ እንደሆነች ፡ ያስረዳው ። በሌላው ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ለአደራ ፡ አስጠባቂዋ ፡ ሊሰጥ ፡ አይደለም ።

፩ሺ፶ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ከአንድ ፡ ሰው ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ ቢያኖሩ ፡ ሁለተኛው ፡ ካልፈቀደ ፡ በቀር ፡ ከእነርሱ ፡ ለአንደኛው ፡ መስጠት ፡ አይገባውም ።

፩ሺ፶፩ አደራ ፡ የሰጡት ፡ ሰው ፡ ባሪያም ፡ ቢሆን ፡ ከብትም ፡ ቢሆን ፡ እስኪሞቱ ፡ ድረስ ፡ ምግብና ፡ መጠጥ ፡ ባይሰጣቸው ፡ በሰዳቸው ፡ ይያዛል ። አደራ ፡ የሰጠው ፡ ምግብ ፡ መጠጥ ፡ አትስጣቸው ፡ ያለው ፡ ቢሆን ፡ ለመፍቅዳቸው ፡ ከገንዘቡ ፡ የሰጣቸውን ፡ ሁሉ ፡ ከባለአደራው ፡ እርሱን ፡ ሊፈልግ ፡ ይገባዋል ። ቢከሰከል ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ በሰጠው ፡ ገንዘብ ፡ ልክ ፡ እንደ ፡ መያዣ ፡ ትሆናለች ። ያንጊዜም ፡ ከሞስነቱ ፡ ትወጣለች ። ስለአደራውና ፡ ሰዳን ፡ ስለመክፈል ፡ ቢጣሉ ፡ ከመሐላው ፡ ጋር ፡ አደራ ፡ እንዳስጠበቀት ፡ ሰው ፡ ቃል ፡ ይሁን ። እርሱ ፡ በገንዘቡ ፡ እምኖታልና ። አደራ ፡ አስቀማጭ ፡ የሚያስረዳ ፡ ምስክር ፡ ቢያመጣ ፡ እንደ ፡ ቃሉ ፡ ይሁን ።

፩ሺ፶፪ ማውጣትና ፡ መቀበልን ፡ ከለመደ ፡ በኋላ ፡ ገንዘቡን ፡ ለመቀበል ፡ የማውጣትና ፡ ከባለቤቱም ፡ የመፈለግ ፡ ሁኔታን ፡ ለለመደ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አደራ ፡ መስጠት ፡ አይገባም ።

፩ሺ፶፫ አደራ ፡ የአስቀመጠበት ፡ ሰው ፡ ቢሞት ፡ ጋኔን ፡ የያዘውም ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ አእምሮው ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፡ አደራ ፡ ትፈርሳለች ።

፩ሺ፶፬ አደራ ፡ የተቀበለውም ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አደራ ፡ አስቀማጩ ፡ እንደሰረቃት ፡ ወይም ፡ በኀይል ፡ እንደቀማት ፡ ቢያውቅ ፡ በአጠፈቃ ፡ ሊከታተሉት ፡ ይገባል ። ለገንዘቡ ፡ እንደሚተጋ ፡ ለአደራውም ፡ ገንዘብ ፡ የማይተጋ ፡ እንዲሁ ፡ ተንኮል ፡ ሥራ ፡ የተስማማ ፡ ሳይሆን ፡ ከዳተኛ ፡ ጨካኝ ፡ ቸልተኛ ፡ እንደመሆኑ ፡ መጠን ፡ አደራ ፡ አስቀማጩ ፡ ይፈልገው ። እንዲሁ ፡ በገንዘብ ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡ ግብር ፡ አለች ።

## አንቀጽ ፴ ።

### በእንተ ፡ ምግብና ።

፩ሺ.፴፮ እምቀኖና ፡ ነገሥት ፡ ወምክር ፡ ዘበእንቲአሃ ። መክ ፡ ፶ወ፯፡ ፡ ዘ፷ወ፩ዱ ፡ ፷ወ፰፡ ፡ ፻ወ፲፡ ፡ ፻ወ፳ ። ወዙሉ ፡ ዘአሠነየ ፡ ሥርዓታ ፡ ለነፍስ ፡ በምንትኒ ፡ ግብር ፡ እምግብራት ፡ ወፍትሕ ታት ፡ ይለዎ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ መጋቤ ፡ በላዕ ሌሆሙ ። ወምግብናስ ፡ ትከውን ፡ ብውሕተ ፡ ላዕለ ፡ ኩሉ ፡ ግብራት ፡ ወፍትሐታት ፡ ወትት አመን ፡ በንዋይ ፡ ጥዩቅ ፡ ዘእንበለ ፡ ካልኡ ፡ ወይትዌከፋ ፡ መጋቢ ፡ በዓስብ ፡ ወዘእንበለ ፡ ዓስብ ። ወሶበ ፡ ተሐጕለ ፡ ንዋየ ፡ አመጋቢ ፡ በእደ ፡ መጋቢ ፡ ዘእንበለ ፡ ጽልሑት ፡ ወአ,ዘ ኬት ፡ ኢይደልዎ ፡ ይፍዲ ። ወኢይትወሆም ፡ ምግብና ፡ ዘእንበለ ፡ በአብሑተ ፡ ቃሉ ፡ ለአመ ጋቢ ፡ ወተወክፎቱ ፡ ቃሉ ፡ ለመጋቢ ፡ አው ፡ በግቢር ።

፩ሺ.፴፯ ወኢይደልዎ ፡ ለመጋቢ ፡ ከመ ፡ ይሢጥ ፡ ምን ተኒ ፡ ንዋየ ፡ በስድሜ ፡ ለእመ ፡ ኢአዘዘ ፡ አመ ጋቢ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ በዝንቱ ፡ እመኒ ፡ በብ ዙኅ ፡ አው ፡ በዘየሐጽጽ ፡ እምሤጡ ። ወለእመ፡ ይቤሎ ፡ ሢጥ ፡ ሊተ ፡ በስድሜ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ይሢጣ ፡ በፍጡን ፡ እመ ፡ ኢነትጎ ፡ ሤጡ ፡ በእ ንተ ፡ ክዊኖቱ ፡ ፍጡን ።

፩ሺ.፴፰ ወኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይሣየጥ ፡ ለአመጋቢሁ ፡ ምንተኒ ፡ እምንዋየ ፡ ብሩር ፡ ካልአ ፡ እምዘ ፡ አዘዘ ፡ በቃሉ ፡ አው ፡ በመልእክቱ ። ወለእመ ፡ ይቤሎ ፡ ተሣየጥ ፡ ሊተ ፡ በ፲፻ት ፡ ፍጡነ ፡ ይደ ልዎ ፡ በስድሜ ፡ ከመ ፡ ይሣየጥ ፡ በ፲፻ት ። ወለ እመ ፡ አኀዘ ፡ እምዘተሣየጠ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ያግብእ ፡ ለአመጋቢሁ ፡ ለዘቦቱ ፡ ንውር ፡ እንዘ ፡ ቦ ፡ በእዴሁ ። ወለእመሰ ፡ መጠዎ ፡ ለአመጋቢሁ ፡ ኢይሚጣ ፡ ካዕበ ፡ ኀቤሁ ፡ ዘእን በለ ፡ በትእዛዙ ።

፩ሺ.፴፱ ወለእመ ፡ ይቤሎ ፡ ተሣየጥ ፡ ሊተ ፡ በንዋይከ ፡ አው ፡ እምዘ ፡ ዚአከ ፡ ዘይሴተ ፡ በ፲፻ት ፡ ወአነሂ ፡ እፈድየከ ፡ በጊዜ ፡ ዘይመጽእ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይሣየጥ ፡ ሎቱ ። ወይኩን ፡ ዘይሴተ ፡ ለአመጋቢ ፡ ወይትመጦብ ፡ ቦቱ ፡ እምድኅረ ፡ አወፈየ ፡ ሤጠ ፡ ዚአሁ ፡ ወ፲፻ት ፡ ይኩን ፡ ለመጋቢ ፡ ለእመ ፡ በጽሐ ፡ ጊዜሁ ፡ ወይኩን ፡ ቅብእ ፡

## አንቀጽ ፡ ፴ ።

### ስለ ፡ ምግብና ፡ (ስለአስተዳደር) ፡ ይናገራል) ።

፩ሺ.፴፮ ከፍትሐ ፡ ነገሥት ፡ ስለእርሷም ፡ ከተነገረው ፡ ምክር ፡ የተገኘ ፡ ነው ። መክ ፡ ፶፯ ፡ ፷፩ ፡ ፷፰ ፡ ፻፲ ፡ ፻፳ ። ከሥራና ፡ ከፍርድ ፡ በማናቸውም ፡ ሥራ ፡ የራሱን ፡ ሥርዓት ፡ ያማመረ ፡ ሁሉ ፡ በእ ነርሱ ፡ ላይ ፡ መጋቢ ፡ (አስተዳዳሪ) ፡ ሊሆን ፡ ይ ገባዋል ። አስተዳዳርስ ፡ በሥራዎችና ፡ በፍር ዶች ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡ የተገባች ፡ ትሆናለች ። ከሌ ላው ፡ በቀር ፡ በተረጋገጠ ፡ ገንዘብ ፡ ትታመናለች፡ መጋቢ ፡ በገንዘብ ፡ ያለገንዘብ ፡ ይቀበላታል ፡ ያለተንኮልና ፡ ያለስንፍና ፡ የአመጋቢ ፡ ገንዘብ፡ በመጋቢ ፡ እጅ ፡ ቢጠፋ ፡ ሊከፍል ፡ አይገባ ውም ። ምግብና ፡ በአመጋቢ ፡ ፈቃድና ፡ በመ ጋቢ ፡ ቃል ፡ መቀበል ፡ ወይም ፡ በሥራ ፡ ካል ሆነ ፡ በቀር ፡ አይጸናም ።

፩ሺ.፴፯ አመጋቢ ፡ በብዙም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ከዋጋው፡ በሚያንስ ፡ በዚህ ፡ እንዲሆን ፡ካላዘዘ ፡ በቀር ፡ ለመጋቢው ፡ በተወሰነ ፡ ጊዜ ፡ (በዱቤ) ፡ ምንም ፡ ገንዘብ ፡ ይሸጥ ፡ ዘንድ ፡ አይገባውም ። በተወሰነ ፡ ጊዜ ፡ (በዱቤ) ፡ ሽጥልኝ ፡ ቢለው ፡ በችኩላ ፡ ስለሆነ ፡ ዋጋው ፡ ካልጎደለ ፡ ፈጥኖ ፡ ሊሸጣት ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፴፰ በቃሉ ፡ ወይም ፡ በመልእክቱ ፡ ካዘዘው ፡ ሌላ ፡ ከብር ፡ ገንዘብ ፡ ሌላ ፡ ለአመጋቢው ፡ ሊገዛ ለት ፡ አይገባውም ። ፈጥነህ ፡ በሽህ ፡ ብር ፡ ግዛ ልኝ ፡ ቢለው ፡ በተወሰነ ፡ ጊዜ ፡ በሽህ ፡ ብር ፡ ሊገዛ ፡ ይገባዋል ። ከገዛው ፡ ገንዘብ ፡ ቢይ ዝም ፡ በእጁ ፡ ሳለ ፡ ነውር ፡ ያለበትን ፡ ለአ መጋቢው ፡ ሊመልስ ፡ ይገባዋል ። ለአመጋ ቢው ፡ ቢሰጠው ፡ ግን ፡ ካላዘዘ ፡ በቀር ፡ ዳግ መኛ ፡ ወደእርሱ ፡ አይመልሳት ።

፩ሺ.፴፱ በገንዘብህ ፡ ወይም ፡ ከአንተ ፡ በሽህ ፡ ብር ፡ ዘይት ፡ ግዛልኝ ፡ እኔም ፡ በሚመጣው ፡ ጊዜ ፡ እከፍልሃለሁ ፡ ቢለው ፡ ሊገዛለት ፡ ይገባዋል ። ዋጋውን ፡ ከከፈለ ፡ በኋላ ፡ ዘይቱ ፡ ለአመጋ ቢው ፡ (ለጌታው) ፡ ይሁን ። ያስተዳድርበትም ። ጊዜው ፡ ከደረሰ ፡ ሽሁ ፡ ብር ፡ ለአስተዳዳሪው ፡ ይሁን ። የዘይቱ ፡ ቅባት ፡ ስለዋጋው ፡ ፈንታ ፡

ዘይኩን ፡ ታሕተ ፡ እደዊሁ ፡ እንዘ ፡ ህየንተ ፡ ማሕፀን ፡ ወለእመ ፡ ተሣየጠ ፡ ሎቱ ፡ በንዋየ ፡ ዚአሁ ፡ ዘእንበለ ፡ የአዝዞ ፡ ይኩን ፡ እንዘ ፡ ታሕተ ፡ እደዊሁ ።

፩ሺ.፴፱ ወለእመኒ ፡ አመነ ፡ በተማይጦ ፡ ንዋይ ፡ እሙር ፡ ኢይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይሣየጦ ፡ ለንፍሱ ፡ ወለኵሉ ፡ ዘተማየጠ ፡ በስመ ፡ ዘአመግበ ፡ ወረደይናደሰ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ በንዋዩ ፡ ኢይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይረስዮ ፡ ለንፍሱ ፡ ዘእንበለ ፡ በመባሕቱ ። ወኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይቀንጽ ፡ ለአመጋቢሁ ፡ ውስተ ፡ ሥምዓ ፡ በዘይወሕድ ፡ እምሤጡ ፡ ወኢበተማይጦ ፡ በዘይበዝኅ ፡ እምኔሁ ፡ በጊዜ ፡ ወመካን ፡ ዘይከውን ፡ በውስቴቱ ፡ ተቋጽሮ ፡ ዘእንበለ ፡ በምዕዜ ፡ ዘተሰነአወ ፡ ቦቱ ፡ ምስለ ፡ ተማያጢ ፡ ወሠያጢ ፡ ዘከመ ፡ ተኃልፎት ፡ ማእከለ ፡ ቀመተ ፡ ማእምራን ፡ ፈደፋደሰ ፡ ተቋጽሮቶን ፡ ምስለ ፡ እሊአሁ ፡ ወወላዲሁ ፡ ወወልዱ ፡ ወወልደ ፡ ወልዱ ፡ ወብእሲቱ ።

በታወቀ ፡ ገንዘብ ፡ ግዥ ፡ መጋቢ ፡ ቢያደርገው ፡ ለራሱ ፡ ሊገዛው ፡ አይገባውም ። በአመጋበው ፡ ስም ፡ የገዛውን ፡ ሁሉ ፡ ይልቁንም ፡ በገንዘቡ ፡ ቢሆን ፡ በፈቃዱ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ለራሱ ፡ ሊያደርገው ፡ አይገባውም ። በሚሸጠው ፡ ከዋጋው ፡ በሚያንስ ፡ በመግዛትም ፡ ከእርሱ ፡ (ከዋጋው ፡) በሚበዛ ፡ በውስጡ ፡ መቆጣጠር ፡ በሚሆንበት ፡ ጊዜና ፡ ቦታ ፡ ለመጋቢው ፡ ሊቆጣጠር ፡ አይገባውም ። ከገዥና ፡ ከሻጭ ፡ ጋራ ፡ በተስማማበት ፡ ልክ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ይኸውም ፡ በአዋቂዎች ፡ ውሳኔ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ መተላለፍ ፡ ያለ ፡ ነው ። ይልቁንም ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋራ ፡ ያሉ ፡ አባቱና ፡ ልጁ ፡ የወንድ ፡ ልጁ ፡ ልጅና ፡ ሚስቱ ፡ ተቆጣጣሪዎች ፡ ናቸው ።

፩ሺ.፵ ወዘወሀበ ፡ ሎቱ ፡ አመጋቢሁ ፡ ፩ደ ፡ ዲናረ ፡ ከመ ፡ ይሣየጥ ፡ ሎቱ ፡ ቦቱ ፡ አሐተ ፡ በግዐተ ፡ ወተማየጠ ፡ ሎቱ ፡ ቦቱ ፡ ፪ተ ፡ አባግዐተ ፡ ዘዘአሐቲ ፡ እምኔሆን ፡ ዘትከውን ፡ ፩ደ ፡ ዲናረ ፡ እማንቱ ፡ ይኩና ፡ ለአመጋቢሁ ። ወለእመ ፡ አመገበ ፡ በሠይጥ ፡ ለብእሲ ፡ በሤጥ ፡ ስሉጥ ፡ ወለእመ ፡ ኢኮነ ፡ መፍትሔ ፡ ዘእንበለ ፡ ሤጥ ፡ ባሕቲቱ ፡ ይለወ ፡ ሤጡ ፡ ለካልኡ ፡ በውእቱ ፡ ንዋይ ፡ እመ ፡ ኮነ ፡ ጥዩቀ ፡ በከዋኔ ፡ ሤጥ ።

መጋቢው ፡ አንዲት ፡ በግ ፡ ይገዛለት ፡ ዘንድ ፡ ፩ ፡ ዲናር ፡ የሰጠው ፡ ሰው ፡ ከእነርሱ ፡ እያንዳንዱ ፡ አንዳንድ ፡ ዲናር ፡ የምትሆን ፡ ፪ ፡ በጎች ፡ በዚያ ፡ ቢገዛለት ፡ እነዚያ ፡ ለአመጋቢው ፡ ይሁኑ ። በታወቀ ፡ ዋጋ ፡ ለሰው ፡ በመሸጥ ፡ መጋቢ ፡ ቢያደርገው ፡ ፈቃዱ ፡ ያለዋጋ ፡ ብቻ ፡ ካልሆነ ፡ በዋጋ ፡ ሁኔታ ፡ የተረጋገጠ ፡ ከሆነ ፡ በዚያው ፡ ገንዘብ ፡ (ዋጋ) ፡ ዋጋው ፡ ለሌላው ፡ ተገባው ።

፩ሺ.፵፩ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ተጋእዞ ፡ ዘአልቦቱ ፡ ስምዐ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለመጋቢ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ነዋ ፡ ተአመነ ፡ ላዕለ ፡ ንዋዩ ። ለእመ ፡ ፈደየ ፡ ዕዳ ፡ ህየንተ ፡ አመጋቢሁ ፡ እንዘ ፡ ኢሀሎ ፡ ውእቱ ፡ ወኢያስምዐ ፡ ላዕለ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ ወእምዝ ፡ ክሕዶ ፡ ውእቱ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ ይደልዎ ፡ ዕዳ ። ወለእመኒ ፡ አማኅፀነ ፡ መጋቢሁ ፡ ንዋየ ፡ ኀበ ፡ ካልእ ፡ ያስምዕ ፡ ለሰማዕት ፡ ቦቱ ፡ ለአመጋቢሁ ፡ ዘአማኅፀኖ ።

ምስክር ፡ የሌለበት ፡ ክርክር ፡ ቢሆን ፡ እንደመጋቢው ፡ ቃል ፡ ይሁን ። እነሆ ፡ እርሱ ፡ በገንዘቡ ፡ አምኖታልና ። እርሱ ፡ ሳይኖር ፡ በአመጋቢው ፡ ፈንታ ፡ ዕዳ ፡ ቢከፍል ፡ ለባለዕዳውም ፡ ባያሰማ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ባለዕዳው ፡ ቢክድ ፡ ዕዳ ፡ ይገባዋል ። መጋቢው ፡ ከሌላ ፡ ሰው ፡ ዘንድ ፡ ገንዘብ ፡ አደራ ፡ ቢያኖር ፡ አደራ ፡ ያስቀመጠው ፡ ገንዘብ ፡ ለአመጋቢው ፡ እንደሆነ ፡ ለምስክር ፡ ያሰማ ።

፩ሺ.፵፪ ወለእመ ፡ ተመገበ ፡ ፩ዱ ፡ ብእሲ ፡ ለ፪ቱ ፡ እደው ፡ በንዋዮሙ ፡ ኢይደልዎ ፡ ለ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ከመ ፡ ይሥራዕ ፡ ውስቴቱ ፡ በባሕቲቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ አምሳለ ፡ አግዕዞ ፡ ገብር ፡ ዘእንበለ ፡ ንሢአ ፡ ቤዛ ፡ ህየንቴሁ ፡ ወኢትእዛዝ ፡ ዘእንበለ ፡ አማኅፀኒሁ ፡ ኀቤሁ ፡

አንድ ፡ ሰው ፡ ለሁለት ፡ ሰዎች ፡ በገንዘብ ፡ መጋቢ ፡ ቢሆን ፡ ከእነርሱ ፡ ለአንዱ ፡ ብቻውን ፡ ሊሠራበት ፡ አይገባውም ። ስለእርሱ ፡ ፈንታ ፡ ዋጋ ፡ ያለመቀበል ፡ ባሪያን ፡ ነፃ ፡ ማውጣትን ፡ የመሰለ ፡ ነገር ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፡ አስቀማጭው ፡ ከሌለ ፡ ወይም ፡

አንቀጽ ፡ ፶ ።

እው ፡ ፈጽሞ ፡ ዕዳ ፡ ዘላዕሌሁ ።

፩ሺ፵፫ ወዘተሣየጠ ፡ ገብረ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይገብር ፡ ዘንተ ፡ ውስተ ፡ መጽሐፍ ፡ ዘተሣየጦ ። ወኢይደልዎ ፡ ለመጋቢ ፡ ከመ ፡ ያመጣብ ፡ ላዕለ ፡ ዘአመገብዎ ፡ ባቲ ፡ ዘእንበለ ፡ ትእዛዘ ፡ እመጋቢሁ ፡ እው ፡ ከመ ፡ ይብጽሕ ፡ ወኢይክልእዎ ፡ እው ፡ በእንተ ፡ ዓጸባ ፡ ከሙት ።

፩ሺ፵፬ ወኢይፃእ ፡ ምግብና ፡ እመጋቢ ፡ ዘእንበለ ፡ በሥምረተ ፡ እመጋቢ ፡ ባሕቲቱ ፡ አላ ፡ እስከ ፡ ይብጽሕ ፡ ከዊን ፡ ወእይወፅእ ፡ እምኔሃ ፡ በፈቃደ ፡ ርእሱ ፡ ዳእሙ ፡ እስከ ፡ የእምር ፡ እመጋቢሁ ፡ ወእስከ ፡ ያወፍዮ ፡ ከመ ፡ ይሥራዕ ፡ በንዋዩ ፡ እው ፡ ከመ ፡ ይረክብ ፡ መጋቢ ፡ ካልአ ፡ በአምሳሊሁ ፡ ወማእከሌ ። ወእምከመ ፡ ወፅአ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ እምግብና ፡ ሥርዓት ፡ በሞት ፡ እው ፡ ለእመ ፡ ቦቱ ፡ መላኪ ፡ በላዕሌሁ ፡ ተሥዕረት ፡ ምግብናሁ ፡ ለእመ ፡ አእመረ ፡ ካልኡ ፡ እው ፡ ኢያእመረ ። ወለእመ ፡ ዐብደ ፡ መጋቢ ፡ ዕበደ ፡ ብዙኀ ፡ እው ፡ ስእነ ፡ ስኢነ ፡ ከሙተ ፡ በአምሳለ ፡ ዑረት ፡ ወዘይመስሎ ፡ በጠለት ፡ ለእመኒ ፡ አእመረ ፡ እመጋቢሁ ፡ እው ፡ ኢያእመረ ።

ስለ ፡ ነፃነትና ፡ ባርነት ።

ዕዳ ፡ ከሌለበት ፡ ማዘዝ ፡ አይገባውም ።

፩ሺ፵፫ ባሪያ ፡ የገዛ ፡ ሰው ፡ ይህን ፡ የገዛውን ፡ በመጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ሊጽፈው ፡ ይገባዋል ። መጋቢ ፡ እርሱን ፡ መጋቢ ፡ በአደረገበት ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡ መጋቢ ፡ ሊሾም ፡ አይገባውም ። በአመጋቢው ፡ ትእዛዝ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ዶርሶ ፡ እስኪመለስ ፡ ወይም ፡ በታወቀ ፡ ጭንቅ ፡ አይከልከሉት ።

፩ሺ፵፬ ምግብና ፡ ያለ ፡ እመጋቢው ፡ ፈቃድ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ከመጋቢው ፡ አይውጣ ። ሁኔታው ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ ነው ፡ እንጂ ። በራሱ ፡ ፈቃድ ፡ ከሹመቱ ፡ አይወጣም ። እመጋቢም ፡ አውቆ ፡ በገንዘቡ ፡ ይሠራበት ፡ ዘንድ ፡ እስኪሰጠው ፡ ድረስ ፡ ወይም ፡ በመሰሉ ፡ ሌላ ፡ መጋቢ ፡ እስኪያገኝ ፡ ድረስ ፡ መቸም ፡ መች ፡ ይቆይ ፡ እንጂ ። ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ በሞት ፡ ከምግብና ፡ ሥርዓት ፡ ቢወጣ ፡ ወይም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡ ገዢ ፡ ቢኖርበት ፡ ሌላው ፡ ቢያውቅም ፡ ባያውቅም ፡ ምግብናው ፡ ትቀራለች ። መጋቢው ብዙ ፡ ስንፍና ፡ ቢሰንፍ ፡ ወይም ፡ የተገለጸ ፡ ድካም ፡ ቢደክም ፡ መታወርና ፡ የመሰለውንም ፡ በመሰለ ፡ ነገር ፡ እመጋቢው ፡ ቢያውቅም ፡ ባያውቅም ፡ ምግብናው ፡ ትቀራለች ።

አንቀጽ ፡ ፶ወ፩ዱ ።

በእንተ ፡ ግዕዛን ፡ ወግብርናት ፡ ወአግዓዝያን ።

፩ሺ፵፭ ወመብዝኅቱኒ ፡ እምቀኖና ፡ ነገሥት ፡ ጠስ ፡ ዘ፹ወ፩ቱ ፡ መከ ፡ ዘ፹ወ፰ቱ ፡ ዘ፹ወ፯ቱ ፡ ዘ፹፯ቱ ፡ ዘ፺ወ፫ቱ ። ወዘተርፈሂ ፡ እምኔሁ ፡ በከመ ፡ ፍትሐ ፡ አእምሮ ፡ ውእቱ ፡ እስመ ፡ ኵሎሙ ፡ ሰብእ ፡ ሱቱፋን ፡ ውስተ ፡ ግዕዛን ፡ በሥርዐ ፡ ፍጥረታዊ ። ወዳእሙ ፡ ጸብእ ፡ ወኀይለ ፡ ፈረስ ፡ ታመጽእ ፡ በሙ ፡ ከመ ፡ ይትቀነዩ ፡ በበይናቲሆሙ ፡ እስመ ፡ ሕገ ፡ ጸብእ ፡ ወመዋኢ ፡ ትረስዮሙ ፡ ለምዉአን ፡ አግብርተ ፡ ለመዋእያን ።

፩ሺ፵፮ ወአሪትኒ ፡ ታጤይቅ ፡ ከመ ፡ ይቅንይዎሙ ፡ ለውፁአን ፡ እምሃይማኖት ፡ ወዘሂ ፡ ተወልዱ ፡ እምኔሆሙ ። እስመ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስቴታ ፡ ዘይብል ፡ ይኩኑ ፡ ለክሙ ፡ አግብርተ ፡ ወአእማተ ፡

አንቀጽ ፡ ፶፩ ።

ስለነፃነት ፡ ስለተገዢነት ፡ ስለ ፡ ነፃ ፡ አውጭዎችም ፡ ይናገራል ።

፩ሺ፵፭ አብዛኛውም ፡ ከፍትሐ ፡ ነገሥት ፡ የተገኘ ፡ ነው ። ጠስ ፡ ፹፩ ። መከ ፡ ፹፰ ። ፹፯ ፡ ፹፯ ፡ ፺፫ ። ከእርሱ ፡ የቀረውም ፡ እንደ ፡ እእምሮ ፡ ፍርድ ፡ (አስተያየት) ፡ ነው ። ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በጥንተ ፡ ተፈጥሮ ፡ በነፃነት ፡ አንድ ፡ ናቸውና ። መጣላትና ፡ የፈረስ ፡ ጉልበት ፡ እርስበርሳቸው ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ (መገዛትን) ፡ ታመጣባቸዋለች ፡ እንጂ ። የጠብና ፡ የማቸነፍ ፡ ሕግ ፡ ድል ፡ የሆኑትን ፡ ድል ፡ ላደረጉት ፡ ባሮች ፡ (ተገዦች) ፡ ታደርጋቸዋለችና ።

፩ሺ፵፮ ኦሪትም ፡ ከሃይማኖት ፡ የወጡትንና ፡ ከእነርሱም ፡ የተወለዱትን ፡ እንዲገዟቸው ፡ ታስረዳለች ። እንዲህ ፡ የሚል ፡ ጽሑፍ ፡ በውስጧ ፡ አለና ። በዙሪያችሁ ፡ ካሉ ፡ ከአሕዛብና ፡ አብረ

እለ ፡ ትነሥእዎሙ ፡ እምአሕዛብ ፡ እለ ፡ ይነ
ብሩ ፡ በዓውድክሙ ፡ ወእምነ ፡ ፈላሲያን ፡ እለ ፡
ይነብሩ ፡ ምስሌክሙ ፡ ወእምኔሆሙ ፡ ተሣ
የጡ ፡ ወእምዘርእሙ ፡ ዘተወልደ ፡ ውስተ ፡
ምድርክሙ ፡ ወይኩኑ ፡ ለክሙ ፡ ዘትወርሰ
ዎሙ ፡ ወለደቂቅክሙ ፡ እምድኅሬሆሙ ።

፩ሺ.፻፺፯ ወኢይደሉ ፡ ሠይጦ ፡ ገብር ፡ ምእመን ፡ ለዘኢየ
አምን ፡ ወውሉዱ ፡ ለገብር ፡ ምልክና ፡ ለመላ
ኪሆሙ ፡ እመኒ ፡ ተወልዱ ፡ እምአግዓዚት ፡
አው ፡ እምአመት ።

፩ሺ.፻፺፰ ወዘወልደ ፡ አመት ፡ ቅኔት ፡ ለመላኪሃ ፡ እመ ፡
ኮነ ፡ እምአግዓዚ ፡ አው ፡ እምገብር ፡ እመሂ ፡
በአውስቦ ፡ እው ፡ እምዘሙት ፡ ዘኢኮነ ፡ እም
እግዚኣ ። ወለእመ ፡ ተግዕዘት ፡ እንዘ ፡ ፅንስት ፡
ይእቲ ፡ ውእቱኒ ፡ ዘውስተ ፡ ከርሣ ፡ ይከውን ፡
ግዑዘ ፡ በእንተ ፡ ዘኮነ ፡ መዋዕለ ፡ ፅንሳ ፡ ኪያሁ፡
እንዘ ፡ ግዕዝት ፡ ይእቲ ፡ ወይደሉ ፡ አግዕዞተ ፡
ዕኑስ ፡ ባሕቲቱ ፡ ዘእንበለ ፡ እንተ ፡ ፀንሰት ፡
ኪያሁ ። ወወልዳ ፡ ለአግዓዚት ፡ እምአግዓዚ ፡
አው ፡ ገብር ፡ ዘአግዓዝዎ ፡ ወእመኒ ፡ መለክዋ ፡
እምድኅረ ፡ ፀንሰት ፡ ኪያሁ ፡ ወእምቅድመ ፡
ትለዶ ፡ እስመ ፡ ለአግዓዚኒ ፡ ኢይዌስኩ ፡ ዲበ ፡
ግዕዛኑ ፡ ግብርናተ ፡ ካልኡ ።

፩ሺ.፻፺፱ ወአግዕዞስ ፡ እምግብረ ፡ ትሩፋት ፡ ይእቲ ፡ ድል
ውት ፡ ከመ ፡ ይግበሩ ፡ ኪያሃ ፡ እስመ ፡ ምጽ
ዋት ፡ ትሩፋት ፡ ይእቲ ፡ ወአብሎተ ፡ ብእሲ ፡
ከመ ፡ ይምልክ ፡ ነፍሶ ፡ በፍትሑ ፡ ጥንቱ ፡
ግዕዘ ፡ ጠባይዓቲሁ ፡ ወኢይትዐወቅ ፡ ጥዮቂሁ ፡
ዘእንበለ ፡ በኀዲገ ፡ መላኪሁ ፡ ወእመኒ ፡ እግ
ዓዞ ፡ በከልእ ፡ ፍኖ ፡ ይደልዎ ፡ ግብኦ ፡ ዜእሁ ፡
እምትድመ ፡ ፍጻሜሁ ። ወለእመ ፡ ተማየጠ ፡
ዳግመ ፡ ይበጽሑ ፡ ፍናዎት ፡ እስከ ፡ ይደግም ፡
ሐድሶቶሙ ፡ ወእመኒ ፡ እግዓዞ ፡ ለጊዜ ፡ ዘት
መጽእ ፡ ኢይደልዎ ፡ ቅንየት ፡ ዘእንበለ ፡
ዘትትለአኮ ፡ እስከ ፡ ጊዜ ፡ ኅዲጎታ ። ወእም
ኔሃ ፡ ባቲ ፡ ትእዛዝ ፡ መኑሉ ፡ ዘተሰንአዋ ፡ እን
ቲእሃ ፡ ወእምነ ፡ ዘኢይትቃወማ ፡ ይደሉ ፡ ዝ ።
ወላእሊሁ ፡ ከመ ፡ ይትለአኮ ፡ ለወልዱ ፡ እምድ
ኅረ ፡ ግዕዛኑ ፡ ዓመታተ ፡ እሙራተ ፡ ወእኮ ፡
ከመ ፡ ይወስን ፡ ላዕሌሁ ፡ ወላስለ ፡ ውሉዱ ፡
ከመ ፡ ይትቀነዩ ፡ ሎቱ ፡ ወለዘርእ ፡ እምዛነ ፡
ሀለወ ። ወይኩኑ ፡ ሎሙ ፡ ኮሉ ፡ ዘአጥረዩ ፡
እስመ ፡ ግብርናት ፡ ትከውን ፡ በዝንቱ ፡ ውሳኔ ።



ዋችሁ ፡ ከሚኖሩ ፡ ከስደተኞች ፡ የምትወስዷ
ቸው ፡ ለእናንተ ፡ ወንዶች ፡ ባሮችና ፡ ሴቶች ፡
ባሮች ፡ ይሁኗችሁ ። ከእነርሱ ፡ በሀገራችሁ ፡
ከተወለደ ፡ ከዘራቸውም ፡ ግዙ ። ለእናንተ ፡
ከእናንተም ፡ በኋላ ፡ ለልጆቻችሁ ፡ የምትወር
ሷቸው ፡ ይሁኑ ።

፩ሺ.፻፺፯ አማኒውን ፡ ባሪያ ፡ ላላመነ ፡ ሰው ፡ መሸጥ ፡
አይገባም ። የባሪያ ፡ ልጆች ፡ ለጌታ ፡ ገንዘቦች ፡
ናቸው ። ከእመቤት ፡ ወይም ፡ ከባሪያዪቱ ፡
ቢወለዱ ።

፩ሺ.፻፺፰ የቤት ፡ ባሪያ ፡ ልጅም ፡ ለጌትዋ ፡ ሊገዛ ፡ ይገ
ባል ። ከጌታ ፡ ወይም ፡ ከባሪያ ፡ የተወለደ ፡
ቢሆን ፡ በጋብቻ ፡ ወይም ፡ ከጌታዋ ፡ ያይደለ ፡
በዝሙት ፡ ቢሆን ፡ ፀንሳ ፡ ሳለች ፡ ነፃ ፡ ብት
ወጣ ፡ እርሱን ፡ የመፅነሷ ፡ ወራት ፡ ነፃ ፡ ሳለች ፡
ስለሆነ ፡ በሆዷ ፡ ያለውም ፡ ሕፃን ፡ ነፃ ፡ ይሆ
ናል ። እርሱን ፡ ከፀነሰችው ፡ በቀር ፡ የተፀነሰ
ውን ፡ ብቻ ፡ ነፃ ፡ ማውጣት ፡ ይገባል ። ከጨዋ፡
የተወለደ ፡ ነፃ ፡ የወጣች ፡ የባሪያ ፡ ልጅ ፡
ወይም ፡ ነፃ ፡ ያወጡት ፡ ባሪያ ፡ እርሱን ፡ ከፀነ
ሰችው ፡ በኋላ ፡ ሳትወልደው ፡ ቢገዟት ፡ ለጌ
ታም ፡ በነፃነቱ ፡ ላይ ፡ የሌላውን ፡ ተገዥነት ፡
አይጨምሩምና ።

፩ሺ.፻፺፱ ከትሩፋት ፡ ወገን ፡ የምትሆን ፡ ነፃ ፡ ማውጣትስ
እርሷን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ የምትገባ ፡ ናት ።
ፍጽምት ፡ ምጽዋት ፡ ናትና ፡ ለሰው ፡ ሥል
ጣን ፡ መስጠትም ፡ በጥንታዊ ፡ የተፈጥሮው ፡
ጠባዩ ፡ ፍርድ ፡ ራሱን ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
በገዢው ፡ መተው ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ዕርግጡ ፡
አይታወቅም ። በሌላ ፡ መንገድ ፡ ነፃ ፡ ቢያወ
ጣው ፡ ነፃ ፡ መውጣቱ ፡ ከመፈጸሙ ፡ አስቀ
ድሞ ፡ ዋጋው ፡ ይገባዋል ። ዳግመኛ ፡ ቢገዛው ፡
እነርሱን ፡ ማደስ ፡ እስኪደግም ፡ ድረስ ፡ ነገሮች
ይቀራሉ ፡ (ይፈርሳሉ) ፡ ለሚመጣው ፡ ጊዜ ፡
ነፃ ፡ ቢያወጣት ፡ እስከሚተዋት ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡
ከምታገለግለው ፡ በቀር ፡ መገዛት ፡ አይገባ
ትም ። ከእርሷም ፡ ትእዛዝ ፡ አለባት ። የተሰ
ማማት ፡ ሁሉ ፡ የእርሷ ፡ ነው ። ከማይቃወ
ማትም ፡ ወገን ፡ ይህ ፡ ይገባል ። ከነፃነቱ ፡
በኋላ ፡ በታወቁ ፡ ዘመኖች ፡ ልጁን ፡ ያገለግ
ለው ፡ ዘንድ ፡ ለእርሱ ፡ ይገባል ። ለእርሱና ፡
ለልጆቹ ፡ ባሉበት ፡ ዘመን ፡ ልክ ፡ ያገለግሉት ፡
ዘንድ ፡ በእርሱ ፡ ላይና ፡ በልጆቹ ፡ ላይ ፡ ሊወ

፩ሺ፶ ወማዕሠንስ ፡ ትትፈጸም ፡ በአማህያነ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እው ፡ በሀልዎቱ ፡ ለሊቀ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ አው ፡ በ፫ቱ ፡ ሰማዕታት ፡ ወትኩን ፡ በመልእክቱ ፡ አው ፡ በጽሒፈ ፡ ትእዛዙ ። ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ በትእዛዙ ፡ ይከውን ፡ ፍትሑ ፡ ዘእሁ ፡ ከመ ፡ ፍትሑ ፡ ተዋርሶ ፡ ወማዕሠንስ ፡ ይከውን ፡ ለኵሉ ፡ አግብርት ፡ አው ፡ በፍልጠት ።

፩ሺ፶፩ ወዘአጥረየ ፡ ፫ተ ፡ አግብርተ ፡ ወአማኅዘ ፡ ፩ደ ፡ ይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ወለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ይሚጥ ፡ እለ ፡ ተርፉ ፡ ይደልዎ ።

፩ሺ፶፪ ወዓዲ ፡ ግዕዛን ፡ ትከውን ፡ ለአግዕዞ ፡ ገብር ፡ ኵለንታሁ ፡ ወለክፍል ፡ እምኔሁ ፡ ወዘሰ ፡ መለከ ፡ ሣልስተ ፡ እደ ፡ እምነ ፡ ገብሩ ፡ ወአግዓዞ ፡ ብጹሕ ፡ ሎቱ ። ወለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ይሢጦ ፡ ኵለንታሁ ፡ ወአግዕዞቶሂ ፡ ይደሉ ፡ ላዕለ ፡ ተሳትፎቱ ፡ በሤጠ ፡ ዘእሁ ፡ በዘኮነ ፡ ወእምከመ ፡ ተሣየጠ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይደልዎ ፡ አግዕዞቱ ፡ ወሤጠ ፡ ቅንዩ ፡ እምሳለ ፡ ንዋይ ፡ በጊዜ ፡ ንበር ፡ ውተባዝኆ ፡ ወሕጸጸ ፡ ወፍድፋዴ ፡ በእምሣነ ፡ ግብረ ፡ እዴ ፡ ወሎጸጼ ፡ ወኢያእምሮቱ ፡ አው ፡ ብዙኅ ፡ ዓመታቲሁ ። ወይደሉ ፡ ተማይጦ ፡ ምእመን ፡ እም እለ ፡ ኢኮኑ ፡ ምእመናን ፡ በዘይደልዎ ፡

፩ሺ፶፫ ወይማዕዝ ፡ ገብር ፡ እምእግዚኡ ፡ በእንተ ፡ ፯ቱ ፡ ግብራት ። ቀዳማዊ ፡ ለእመ ፡ ቀንዮ ፡ ፩ዱ ፡ እምወላዲያኒሁ ፡ ወእምእለ ፡ ተደምሮሙ ፡ እው ፡ ለእመ ፡ ቀንዮ ፡ ፩ዱ ፡ እምውሉዶሙ ፡ ወእለ ፡ እምድኅረሆሙ ፡ አው ፡ ፩ዱ ፡ እምአኃዊሁ ፡ አው ፡ ፩ዱ ፡ እምእለ ፡ ይወርስዎ ፡ ይደልዎሙ ፡ አግዕዞቱ ። ወለእመ ፡ መለከ ፡ ክፍለ ፡ እምኔሁ ፡ አው ፡ ፱ ፡ ካልእ ፡ ዘይመልኮ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ውእቱ ፡ ባዕለ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይማይጥ ፡ ኵለንታሁ ፡ ወያግዕዞ ፡ ኵለንታሁ ።

፩ሺ፶፬ ወዳግም ፡ ለእመ ፡ ተወክፈ ፡ ውእቱ ፡ አው ፡ ብእሲቱ ፡ በጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡ አው ፡ ወለቱ ፡ በአእምሮ ፡ ወላዲያኒሁ ፡ አው ፡ ኮነ ፡ ከሃሁ ፡ በፈቃደ ፡ እግዚኡ ፡ አው ፡ ኮነ ፡ መነኮሰ ፡ ይደሉ ፡ እንከ ፡ አግዕዞቱ ።

፩ሺ፶፭ ሣልስ ፡ ለእመ ፡ ረሰዮ ፡ ሐራዊ ፡ ይደሉ ፡



ስን ፡ እይደለም ። የገዙት ፡ ሁሉ ፡ ስእንርሱ ፡ ይሁን ። ባርነት ፡ በዚህ ፡ ውሳኔ ፡ ትሆናለችና ።

፩ሺ፶ ነፃነትስ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ እለቃው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ወይም ፡ ፫ ፡ ምስክሮች ፡ ባሉበት ፡ በግልጽ ፡ ትፈጸማለች ። በደብዳቤው ፡ ወይም ፡ ትእዛዙን ፡ በመጻፍ ፡ ትሁን ። በትእዛዙ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ፍርዱ ፡ እንደ ፡ መወራረስ ፡ ፍርድ ፡ ይሆናል ። ነፃነትስ ፡ ለባሪያዎች ፡ ሁሉ ፡ ወይም ፡ በመለየት ፡ ይሆናል ።

፩ሺ፶፩ ፫ ፡ ባሮች ፡ የገዛ ፡ ሰው ፡ እንዱን ፡ ነፃ ፡ ቢያወጣው ፡ ይገባዋል ። የቀሩትንም ፡ ሊሸጥ ፡ ቢወድ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፶፪ ዳግመኛም ፡ የባሪያን ፡ ሁለመናውን ፡ ከእርሱም ፡ በክፊል ፡ ነፃ ፡ ማውጣት ፡ ትሆናለች ። ከባሪያው ፡ ሦስት ፡ እጅ ፡ የገዛ ፡ ሰው ፡ ነፃም ፡ ሊያወጣው ፡ ቢወድ ፡ መብትቱ እለው ፡ በሙሉ ፡ ሊሸጠው ፡ ነፃም ፡ ሊያወጣው ፡ ቢወድ ፡ በሆነው ፡ በዋጋው ፡ ሊስማማ ፡ ይገባል ። ከእነርሱም ፡ ቢገዛ ፡ ነፃ ፡ ሊያወጣው ፡ ይገባዋል ። የተገዢውም ፡ ዋጋ ፡ በታወቀ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ገንዘብነቱ ፡ ነው ። ሊበዛና ፡ ሊያንስ ፡ በእጁ ፡ ሥራ ፡ ልክ ፡ መብዛትና ፡ ማነስ ፡ እንዳለማወቁ ፡ ወይም ፡ እንደዕድሜው ፡ መብዛት ፡ ነው ። አማኒውን ፡ (ባሪያ) ፡ ካላመኑት ፡ ሰዎች ፡ በሚገባው ፡ መግዛት ፡ ይገባል ።

፩ሺ፶፫ ባሪያ ፡ ከጌታው ፡ ስለ ፡ ፯ ፡ ሥራዎች ፡ ነፃ ፡ ይወጣ ። መጀመሪያው ፡ ከወላጆቹ ፡ ከተደመሩቸውም ፡ (ካያቶቹ) ፡ እንዱ ፡ ቢገዛው ፡ ወይም ፡ ከልጆቻቸውና ፡ ከእነርሱም ፡ ቀጥሎ ፡ ካሉት ፡ (ከልጅ ፡ ልጆቻቸው) ፡ እንዱ ፡ ቢገዛው ፡ ወይም ፡ ከወንድሞቹ ፡ እንዱ ፡ ወይም ፡ ከወራሾቹ ፡ ወገን ፡ እንዱ ፡ ቢገዛው ፡ ነፃ ፡ ማውጣቱ ፡ ይገባቸዋል ። ከእርሱ ፡ በከፊል ፡ ቢገዛው ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ የሚገዛው ፡ ቢኖር ፡ እርሱ ፡ ባለጸጋ ፡ ከሆነ ፡ በሙሉ ፡ ገዝቶ ፡ በሙሉ ፡ ነፃ ፡ ሊያወጣው ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፶፬ ሁለተኛው ፡ እርሱ ፡ ወይም ፡ ሚስቱ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ልጁ ፡ ወላጆቹ ፡ እውቀው ፡ በጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡ ቢቀበሉት ፡ ወይም ፡ በጌታው ፡ ፈቃድ ፡ ካህን ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ መነኩሴ ፡ ቢሆን ፡ ነፃ ፡ ማውጣቱ ፡ ይገባል ።

፩ሺ፶፭ ሦስተኛው ፡ ወታደር ፡ ቢያደርገው ፡ ነፃ ፡ ማው

እግዐዞቱ ።

፩ሺ.፶፮ ወራብዕሂ ፡ ለእመ ፡ አድኀኖ ፡ ለእግዚኡ ፡ እምቀትል ፡ እመሂ ፡ በተቃትሎቱ ፡ ዘየንተቱ ፡ አው ፡ እምክር ፡ ከመ ፡ ይትዐቀብ ፡ ያግዕዞ ፡ በፍዳሁ ።

፩ሺ.፶፯ ወኃምስሂ ፡ ለእመ ፡ አግዐዘዋ ፡ ለዕንስት ፡ ወለዳኒ ፡ ግዑዝ ፡ ውእቱ ።

፩ሺ.፶፰ ወሳድስሂ ፡ ለእመ ፡ ተአሰረ ፡ ገብር ፡ ወተመይጠ ፡ ኀበ ፡ እግዚኡ ፡ በፈቃዱ ፡ እምድኅረ ፡ ጸንዐ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ጸላኢ ፡ ይደልዎ ፡ ግዕዛን ።

፩ሺ.፶፱ ወሳብዕሂ ፡ ለእመ ፡ ሞተ ፡ እግዚኡ ፡ ወአልቦ ፡ ዘይወርሶ ፡ ዘእንበለ ፡ እግዝእቱ ፡ ወቤተ ፡ መንግሥት ፡ ይደልዎ ፡ ግዕዛን ።

፩ሺ.፷ ወዘእግዐዘ ፡ ገብረ ፡ በእንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ አው ፡ በእንተ ፡ እይኒ ፡ ገጽ ፡ እምገጸት ፡ እመ ፡ ኮነ ፡ ፍቁረ ፡ አው ፡ ጽሉእ ፡ ይደልዎ ፡ ግዕዛን ።

፩ሺ.፷፩ ወዘሂ ፡ ተአመነ ፡ እምግዑዛን ፡ በረቀ ፡ ቅንየት ፡ ለካልኡ ፡ ወፈቀደ ፡ ከመ ፡ ይሠየጥ ፡ ወለእመ ፡ ኀለፈ ፡ መዋዕሊሁ ፡ እምኍ ፡ ዓመት ፡ ወተዓገሠ ፡ ላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ ተአምኖ ፡ እስከ ፡ ይሠይጦ ፡ አው ፡ ይራስዮ ፡ ሕጌ ፡ ሰብእሲቱ ፡ ይከውን ፡ ገብረ ። ወፈድፋደሰ ፡ ሶበ ፡ ተነግረ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ተሰነአወ ፡ ምስለ ፡ ዘሠየጦ ፡ ላዕለ ፡ ሤጠ ፡ ዚአሁ ። ወእመሰ ፡ ኢበጽሐ ፡ ኀበ ፡ ዝንቱ ፡ ዓመታት ፡ ድልው ፡ ለፈታሒ ፡ ወለመኰንን ፡ ከመ ፡ ያውፅእዎ ፡ እምእዴሁ ፡ ወእምእደ ፡ ዘተሣየጠ ፡ እምኔሁ ፡ ወይኩን ፡ ግዑዘ ።

፩ሺ.፷፪ ወይደሉ ፡ ለገብር ፡ ዘእግዓዝዎ ፡ ከመ ፡ ይትመየጥ ፡ ውስተ ፡ ቅንየቱ ፡ ሶበ ፡ ተጠየቀ ፡ ቦቱ ፡ ኀበ ፡ ፈታሒ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ረገሞ ፡ ለእግዚኡ ወዘበጦ ፡ አው ፡ ዘበጦሙ ፡ ለውሉዱ ፡ ዘእንበለ ፡ ሥምረቱ ፡ አው ፡ እኅጕለ ፡ ንዋዮ ፡ በእደ ፡ ካልኣን ፡ ፈቂዶ ፡ ከመ ፡ ያሕሥም ፡ ላዕሌሁ ። ወፈድፋደሰ ፡ እመ ፡ ገብረ ፡ ሕሠመ ፡ ላዕለ ፡ ሕይወቶሙ ፡ ይደልዎ ፡ በከመ ፡ ተአዘዘ ፡ በኦሪት ። ወኢይኅድጎ ፡ እግዚኡ ፡ በግዕዛኑ ፡ ወይፃእ ፡ ከዊኖ ፡ ዕሩቀ ፡ እምብዕሉ ።

፩ሺ.፷፫ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ትትወሰብ ፡ አግዓዚት ፡ ለገብር ፡ ወትንበር ፡ ኀቤሁ ፡ በቤተ ፡ እግዚኡ ፡ አው ፡ ታንብሮ ፡ ኀቤሃ ፡ በፈቃደ ፡ እግዚኡ ፡ ወእመሰ ፡ ትከውን ፡ ይእቲ ፡ ከማሁ ፡ ውስተ ፡



ጣቱ ፡ ይገባል ።

፩ሺ.፶፮ አራተኛው ፡ ጌታውን ፡ ከሞት ፡ ቢያድነው ፡ ስለእርሱ ፡ በመዋጋትም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ እንዲጠነቀቅ ፡ ቢመክረው ፡ ብድሩን ፡ (ዋጋውን) ፡ ነፃ ፡ ያውጣው ።

፩ሺ.፶፯ አምስተኛውም ፡ የፀነሰችውን ፡ ባሪያ ፡ ነፃ ፡ ቢያወጧት ፡ ልጅዋም ፡ ነፃ ፡ ነው ።

፩ሺ.፶፰ ስድስተኛውም ፡ ባሪያ ፡ ቢታሠር ፡ በጠላት ፡ እጅ ፡ ከቆየ ፡ በኋላ ፡ በፈቃዱ ፡ ወደጌታው ፡ ቢመለስ ፡ ነፃነት ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፶፱ ሰባተኛውም ፡ ጌታው ፡ ቢሞት ፡ ከእመቤቱና ፡ ከቤተ ፡ መንግሥት ፡ በቀር ፡ ወራሽ ፡ ባይኖረው ፡ ነፃነት ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፷ ባሪያውን ፡ ስለእግዚአብሔር ፡ ብሎ ፡ ከምክንያቶች ፡ በማናቸውም ፡ ምክንያት ፡ ነፃ ፡ ያወጣ ፡ ሰው ፡ የሚወደውም ፡ ወይም ፡ የሚጠላው ፡ ቢሆን ፡ ነፃነት ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፷፩ ነፃ ፡ ከሚወጡት ፡ ባሮች ፡ በመገዛት ፡ ደብዳቤ ፡ ለሌላው ፡ ቢያምን ፡ ሊሸጥም ፡ ቢወድ ፡ ዕድሜዉም ፡ ከኻያ ፡ ዓመት ፡ ቢያልፍ ፡ እስኪሸጠው ፡ ወይም ፡ ለሚስቱ ፡ ማጫ ፡ እስኪያደርገው ፡ ድረስ ፡ በዚህ ፡ በማመኑ ፡ ቢታገሥ ፡ (ቢፀና) ፡ ባሪያ ፡ ይሆናል ። ይልቁንም ፡ ከሸጠው ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ በዋጋው ፡ እንደተስማማ ፡ በተነገረ ፡ ጊዜ ። ወደዚህ ፡ ዓመት ፡ (ኻያ ፡ ዘመን) ፡ ባይደርስ ፡ ግን ፡ ለዳኛና ፡ ለገዢ ፡ ከእጁና ፡ ከእርሱ ፡ ከገዛውም ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ሊያወጡት ፡ አገባብ ፡ ነው ። ነፃም ፡ ይሁን ።

፩ሺ.፷፪ ነፃ ፡ ያወጡት ፡ ባሪያ ፡ ጌታውን ፡ እንደረገመውና ፡ እንደመታው ፡ ወይም ፡ ልጆቹን ፡ ያለፈቃዱ ፡ እንደመታቸው ፡ ወይም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ሊያደርግ ፡ ወዶ ፡ በሌሎች ፡ እጅ ፡ ገንዘቡ ፡ እንደጠፋበት ፡ በዳኛ ፡ ዘንድ ፡ ቢመሰከርበት ፡ ወደመገዛቱ ፡ ሊመለስ ፡ ይገባል ። ይልቁንም ፡ በሕይወታቸው ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ቢሠራ ፡ በኦሪት ፡ እንደታዘዘው ፡ ይገባዋል ። ጌታው ፡ በነፃነቱ ፡ አይተወው ። ከሀብቱ ፡ ባዶ ፡ ሁኖ ፡ ይውጣ ።

፩ሺ.፷፫ ነፃ ፡ የወጣች ፡ ባሪያ ፡ ለባሪያ ፡ ሚስት ፡ ልትሆን ፡ በጌታውም ፡ ቤት ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ ልትኖር ፡ ወይም ፡ በጌታው ፡ ፈቃድ ፡ በእርሱዋ ዘንድ ፡ ልታኖረው ፡ አይገባም ። ያንጊዜ ፡ እር

ግብርናት ፡ ለእግዚኡ ።

፩ሺ፰፻፬ ወዘኒሁ ፡ ለገብረ ፡ ካልኡ ፡ ዘኢኮነ ፡ ሎቱ ፡ ወኀብአ ፡ ወአርኀቆ ፡ ይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ መይጦቱ ፡ ገብር ፡ ለእግዚኡ ፡ ወይወስክ ፡ ላዕሌሁ ፡ ካልአ ፡ ገብረ ፡ አው ፡ ሤጦ ። ወከማሁ ፡ ዘአኅደረ ፡ ገብረ ፡ ካልኡ ፡ ዘኢኮነ ፡ ሎቱ ፡ ወረሰዮ ፡ ገብረ ፡ ለርእሱ ፡ እንዘ ፡ የአምር ፡ ከመ ፡ ውእቱ፡ ኮነ ፡ ገብረ ፡ ካልኡ ፡ ውእቱ ፡ አሚሃ ፡ ይኩን ፡ ከማሁ ፡ በውስተ ፡ ግብርናት ፡ ለዘ ፡ በእማን ፡ እግዚአ ፡ ዚአሁ ።

ቢሆም ፡ እንደእርሱ ፡ ለጌታው ፡ በተገዥነት ፡ ውስጥ ፡ ትሆናለች ።

፩ሺ፰፻፬ የእርሱ ፡ ያልሆነውን ፡ የሌላውን ፡ ባሪያ ፡ ያባበለ ፡ አርቆም ፡ የሸሸገ ፡ ሌላ ፡ ሁለተኛ ፡ ባሪያ ፡ ወይም ፡ ዋጋውን ፡ ጨምሮ ፡ ለጌታው ፡ ሊመልሰው ፡ ይገባል ። እንደዚኸውም ፡ የእርሱ ፡ ያልሆነውን የሌላውን ፡ ባሪያ ፡ ያሳደረ ፡ የሌላው ፡ ባሪያ ፡ እንደሆነም ፡ እያወቀ ፡ ለራሱ ፡ ባሪያ ፡ ያደረገው ፡ ያንጊዜ ፡ እርሱ ፡ ለዕውነተኛው ፡ ጌታው ፡ በባርነት ፡ እንደእርሱ ፡ ይሁን ።

---

## አንቀጽ ፡ ፴ወ፪ቱ ።

በእንተ ፡ ምግብና ።

፩ሺ፰፻፰ ዘአምጽእዎ ፡ እምአብጥሊስ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ወዘይደሉስ ፡ ለምግብና ፡ ፪ቱ ፡ ግብራት ። ቀዳማዊ ፡ ለዘኢይትኀሠሎ ፡ ያእምር ፡ ዘውስተ ፡ ልቡ ፡ ዘይደሉ ፡ ለፍጻሜ ፡ ጠባይዕ ፡ ወዘይሤኒ፡ ለሥምረቱ ፡ እመኒ ፡ በምክንያተ ፡ ጋኔን ፡ ዘያጌብሮ ፡ ወዝንቱ ፡ ዐብድ ፡ ውእቱ ። አው ፡ በአማስኖ ፡ ናላሁ ፡ በደዌ ፡ ወዝንቱኒ ፡ ዝንጉዕ፡ ውእቱ ፡ ዘቀደሙት ፡ ግብሩ ፡ አው ፡ ሶበ ፡ ኢበጽሐ ፡ ናላሁ ፡ ፍጹመ ፡ ወዝንቱኒ ፡ ሕፃን ፡ ውእቱ ፡ ዘኢበጽሐ ፡ እስከ ፡ ፲ወ፰ቱ ፡ ዓመት ። አው ፡ እስመ ፡ ቀዳሚት ፡ ግብሩ ፡ ለእመ ፡ ይከመት ፡ በጠባይዕ ፡ እንዘ ፡ ይትጌበር ፡ ባቲ ፡ ወውእቱ ፡ ድኅረ ፡ ልህቀ ፡ ወቀርበ ፡ ኀበ ፡ ፶ቱ ፡ ዓመት ፡ ወቀዳሚት ፡ ግብሩ ፡ ኮነት ፡ ድኅንተ ፡ ወፍጽምተ ፡ ወባሕቱ ፡ ኢተገበረ ፡ ባቲ ፡ በዘይደልዋ ፡ ወውእቱ ፡ ስሑን ። አው ፡ እመ ፡ ውእቱ ፡ ተገብረ ፡ ባቲ ፡ ግብረ ፡ በዘያሐሥም ፡ በዝንቱ ፡ ዓለም ፡ ወያኅሥሣ ፡ ወዝንቱኒ ፡ እንዝህሉል ፡ ውእቱ ፡ በሥርዓቱ ፡ ወንዋዩ ፡ ዘከመ ፡ ዘሬዊ ፡ በአስተዋፅኦታት ፡ ወአጥፍአ ። ወዝንቱኒ ፡ ይትዓቀብ ፡ በጽኑዕ ፡ ከመ ፡ ካዕበ ፡ እንዝኅሉለ ፡ ኢይኩን ፡ በውስተ ፡ ሃይማኖቱ ፡ በሰቢስ ፡ ሕርመታት ፡ ወአብዝኆ ፡ ፍትወታት ፡ ወዜናሁስ ፡ ለእንዝኅሉል ፡ ይትናጸር ፡ ምስለ ፡ ዜናሁ ፡ ለልብዘው ።

## አንቀጽ ፡ ፴፪ ።

ስለ ፡ አስተዳደር ፡ ይናገራል ።

፩ሺ፰፻፰ ከአብጥሊስና፡ከሚመስለውም፡ያመጡት፡ነው። ለአስተዳደር፡የሚገቡስ፡፪፡ሥራዎች፡ናቸው ። መጀመሪያው ፡ ለፍጹም፡ባሕርዩ፡የሚገባውንና ለፈቃዱ፡የሚስማማውን፡በልቡ፡ውስጥ ፡ ያለውን፡ሊያውቅ፡ለማይቻለው፡ሰው ፡ ነው ። በሚጥለው፡ጋኔን፡ምክንያትም፡ቢሆን ፡ ይህም ፡ ዐላዋቂ፡ነው። ወይም፡በደዌ ፡ አእምሮውን፡በማጣት፡ይኸውም፡የቀደመች፡ሥራውን ፡ የሚዘነጋ፡ነው። ወይም፡አእምሮው፡ወደፍጹምነት ፡ ያልደረሰ፡ይኸውም ፡ እስከ ፡ አሥራስምንት ፡ ዓመት፡ያልደረሰ፡ሕፃን፡ነው። ወይም፡የመጀመሪያዪቱ፡ሥራው፡እየሠራበት፡በባሕርይ ፡ ብትደክም፡ይኸውም፡ሽምግሎ፡ወደ ሃ፡ዓመት ፡ ስለቀረበ፡ነው። የቀደመች፡ግብሩም፡ደኅና፡ፍጽምት፡ነበረች። ነገር፡ግን፡በሚገባት ፡ አልሠራባትም። ይኸውም፡ደካማ፡ነው። ወይም ፡ በዚህና፡በኋለኛው፡ዓለም፡የሚጎዳ ፡ ሥራ፡ቢሠራባት፡ይኸውም ፡ በሥርዓቱና ፡ (በአስተዳደሩ ፡) በገንዘቡ ፡ ንዝኅላል ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በማወጣጣትና ፡ በማጥፋት ፡ ገንዘቡን ፡ እንደሚበትን ፡ ነው ። ይህም ፡ የተከለከለውን ፡ በመልበስና ፡ ዝሙትን ፡ በማብዛት ፡ ዳግመኛ ፡ በሃይማኖት ፡ ንዝኅላል ፡ እንዳይሆን ፡ በጽኑ ፡ ይጠበቅ ። የንዝኅላል ፡ ሰው ፡ አስተያየት ፡ ከአስተዋይ ፡ ሰው ፡ አስተያየት ፡ ጋራ ፡ ይነፃፀራል ።

አንቀጽ ፡ ፴፪ ።

፩ሺ፳፮ ወማብርኒ ፡ ዳግማዊ ፡ ዘይከልእ ፡ ለለባዊ ፡ መግቦተ ፡ ርእሱ ፡ በንዋዩ ፡ ወውእቱ ፡ ገብር ። ወለዘሂ ፡ ሀለወ ፡ በታሕተ ፡ ምግብና ፡ እመ ፡ ኮነ ፡ ሀብዪ ፡ አው ፡ ዝንጉዐ ፡ አው ፡ ሕፃን ፡ ንኡስ ፡ አው ፡ አረጋዊ ፡ ዘረስዐ ፡ በመዋዕሊሁ ። ኢይደልዎሙ ፡ ለእሉ ፡ ከመ ፡ ይሥርዑ ፡ ኢ ፡ በእስተዋስቦ ፡ ወኢ ፡ በተአምኖ ፡ ቃል ፡ ኢ ፡ ለነፍሶሙ ፡ ወኢ ፡ ለካልኣኒሆሙ ። ወእመኒ ፡ ኮነ ፡ የዋሀ ፡ አው ፡ እንዝንጉለ ፡ ይለዎ ፡ ከመ ፡ ይትመገብ ፡ በንዋዩ ፡ ርእሱ ፡ ወእኩ ፡ ንዋዩ ፡ ካልእ ፡ በትእዛዘ ፡ እመጋቢሁ ፡ ባሕቲቱ ።

፩ሺ፳፯ ወለእመኒ ፡ ገብር ፡ ውእቱ ፡ ይደሉ ፡ መግቦቱ ፡ በትእዛዘ ፡ እግዚኡ ፡ ባሕቲቱ ፡ ወይደልዎ ፡ እምድኅረ ፡ ግዕዛን ፡ ከመ ፡ ይእመን ፡ ባሰለ ፡ ነፍሱ ፡ በከዊነ ፡ ግብርናት ። ወለእሉ ፡ ሶበ ፡ አጥፍኡ ፡ ምንተኒ ፡ እምንዋዮሙ ፡ ይደልዎሙ ፡ ይፍድዩ ። ወለእመ ፡ አዘዘ ፡ ዘሀሎ ፡ ታሕተ ፡ ምግብና ፡ በደዌሁ ፡ ትእዛዘ ፡ ሠናየ ፡ ሕጋዊተ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ሀብዩ ፡ አው ፡ ዝንጉዐ ፡ ኮነት ፡ አማን ፡ ትእዛዞሙ ፡ እምድኅረ ፡ ሞቶሙ ። ወለእመኒ ፡ ኮኑ ፡ ካልኣኒሆሙ ፡ ኢይከውን ፡ አማን ፡ እምኔሃ ፡ ዘእንበለ ፡ ዘይፈጽሞ ፡ መኰንን ፡ ወፈታሒ ።

፩ሺ፳፰ ወመጋቢኒ ፡ ውእቱ ፡ አብ ፡ ለእመ ፡ ኢሀለወ ፡ ታሕተ ፡ ምግብና ፡ ወእምዝ ፡ ዘይሚግብ ፡ አብ ፡ ወእምዝ ፡ እኁ ፡ ዐቢይ ፡ ወእምዝ ፡ እምኔሁ ፡ ወእምዝ ፡ እኁወ ፡ አብ ፡ ወእምዝ ፡ ወልደ ፡ እኁወ ፡ አብ ፡ ወዘይከውን ፡ ለባዊ ፡ እምእል ኵሉ ፡ ኵሎሙ ፡ ይቀድም ፡ እምካልኡ ። ወዘማስን ፡ ልቡ ፡ ወሎቱ ፡ ወልድ ፡ ኅሩይ ፡ ውእቱ ፡ ድልው ፡ እምዝኩራን ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ምግብና ፡ በላዕሌሁ ። ወእምድኅረ ፡ እሉ ፡ ኵሎሙ ፡ አብ ፡ በንብረት ፡ ዘውእቱ ፡ ሐፃኒ ፡ ወለእመ ፡ ኢተረክበ ፡ ፩ዱኒ ፡ እምእለ ፡ ተዘከሩ ፡ ፈታሒ ፡ ይሢም ፡ መጋቢ ፡ ምእመነ ፡ ዘይበቍዕ ፡ ወያፈርሆ ፡ ኪያሁ ።

፩ሺ፳፱ ወኢይደልዎ ፡ ለዘተሠይመ ፡ መጋቤ ፡ ከመ ፡ ይሢጥ ፡ ምንተኒ ፡ ንዋዩ ፡ ዘእንበለ ፡ ሥዩም ፡ ዘእምታሕቴሁ ፡ ወዘእንበለ ፡ በአምጣነ ፡ ሤጡ

ስለ ፡ ምግዚትነት ።

፩ሺ፳፮ ሁለተኛው ፡ ግብር ፡ ዐዋቂን ፡ በገንዘቡ ፡ ራሱን ከማስተዳደር ፡ የሚከለክለው ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ባሪያ ፡ ነው ። በመተዳደር ፡ ስር ፡ ያለ ፡ ዐላዋቂ ፡ ወይም ፡ ዝንጉዕ ፡ ወይም ፡ ትንሽ ፡ ሕፃን ፡ ወይም ፡ በዘመኑ ፡ ያረጀ ፡ ሽማግሌ ፡ ቢሆን ፡ ለእነዚህ ፡ በማጋባት ፡ ለራሳቸውም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ለሌሎቹ ፡ በቃል ፡ መተማመን ሊሠሩ ፡ አይገባቸውም ። አላዋቂ ፡ ወይም ፡ ንዝ ኅላል ፡ ቢሆን ፡ በሌላው ፡ ገንዘብ ፡ ያይደለ ፡ በራሱ ፡ ገንዘብ ፡ በአስተዳዳሪው ፡ ትእዛዝ ፡ ብቻ ፡ ሊተዳደር ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፳፯ ባሪያ ፡ ቢሆንም ፡ በጌታው ፡ ትእዛዝ ፡ ብቻ ፡ ሊተዳደር ፡ ይገባዋል ። ከነፃነትም ፡ በኋላ ፡ በባ ርነት ፡ ሁኔታ ፡ በራሱ ፡ ሊያምን ፡ ይገባዋል ። እሊህም ፡ ከገንዘባቸው ፡ አንዳች ፡ ቢያጠፉ ፡ ሊከፍሉ ፡ ይገባቸዋል ። በመተዳደር ፡ ስር ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ በደዌው ፡ ጊዜ ፡ ሕጋዊ ፡ የሆነ ፡ መልካም ፡ ትእዛዝ ፡ ቢያዝ ፡ አላዋቂ ፡ ዝንጉዕ ፡ ቢሆንም ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ ትእዛዛቸው ፡ የታመ ነች ፡ ሆነች ። እንደነርሱም ፡ ያሉ ፡ ቢሆኑ ፡ ገዥና ፡ ዳኛ ፡ ከሚፈጽመው ፡ በቀር ፡ ከእርሱ ፡ የተነሣ ፡ እውነተኛ ፡ አትሆንም ።

፩ሺ፳፰ አባትም ፡ በመተዳደር ፡ ስር ፡ ካልኖረ ፡ አስተ ዳዳሪ ፡ ነው ። ቀጥሎም ፡ የሚያስተዳድር ፡ አባት ፡ ከዚያም ፡ ቀጥሎ ፡ ታላቅ ፡ ወንድም ፡ ከዚያም ፡ ቀጥሎ ፡ እያት ፡ ከዚያም ፡ ቀጥሎ ፡ ያባት ፡ ወንድም ፡ (አጎት) ፡ ከዚያም ፡ ቀጥሎ ፡ የአባት ፡ የወንድም ፡ ልጅ ፡ (የጎት ፡ ልጅ ፡ ነው ። ከእነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ዐዋቂ ፡ የሆነው ፡ ሰው ፡ ከሌላው ፡ ይቀድማል ። አእምሮው ፡ የጠፋ ፡ ሰው ፡ የተመረጠ ፡ ልጅ ፡ ቢኖረው ፡ ከተነገሩት ሰዎች ፡ ይልቅ ፡ አስተዳደር ፡ ለእርሱ ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ። ከእነዚህ ፡ ሁሉ ፡ በኋላ ፡ በንብረት ፡ ላይ ፡ የሚያዝ ፡ አባት ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ሞግ ዚት ፡ ነው ። ከተነገሩት ፡ ሰዎች ፡ አንድ ፡ እንኳ ፡ ባይገኝ ፡ ዳኛ ፡ የሚጠቅም ፡ የታመነ ፡ ሰው ፡ ይሾም ። እርሱንም ፡ ይጠብቅ ፡ (ይቆ ጣጠር) ።

፩ሺ፳፱ አስተዳዳሪ ፡ ሆኖ ፡ ለተሾመ ፡ ሰው ፡ ከበታቹ ፡ ከተሾመው ፡ ጋር ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ባስቀመጠ በት ፡ ጊዜ ፡ በነበረው ፡ ዋጋ ፡ ልክ ፡ ካልሆነ ፡

በጊዜ ፡ እንበረ ፡ ወኢከመ ፡ ይድፍር ፡ በንዋዩ ፡ በንጊድ ፡ እው ፡ በሠይጥ ፡ በዕድሜ ፡ ዘእንበለ ፡ በእኂዞተ ፡ ክሡተ ፡ ወበዋሕስ ። ወኢይለቅሕ ፡ ምንተኒ ፡ እምኔሁ ፡ አላ ፡ ለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ነጊደ ፡ ወጽሕቀ ፡ ይደልዎ ፡ በግብር ፡ ከመ ፡ ያንብሮ ፡ ማኅፀንተ ፡ እበመ ፡ ሊቃሕ ፡ ለባዕል ፡ በትሕቢት ፡ እው ፡ በእኀዝ ፡ ይኄይስ ፡ እምእ ማኅፀኖት ፡ ለእመ ፡ ተበነእዉ ፡ ተለቃሒ ፡ ወተ ማኅፃኒ ፡ ኀቢሁ ። ማኅፀንትስ ፡ በእንተ ፡ ተአ ምኖቱ ፡ ወተዓቅቦቱ ፡ ለዘይሁብዎ ፡ እበመ ፡ ለተለቃሒ ፡ ቦቱ ፡ ተሐባዪ ፡ በኵሉ ፡ ግብር ፡ ወዘእዐቀብዎስ ፡ ማኅፀንተ ፡ እኮ ፡ ከማሁ ።

፩ሺ.፸ ወለእመ ፡ ተናፈቀ ፡ ዘሀሎ ፡ ታሕተ ፡ ምግብና ፡ ምስለ ፡ መጋቢሁ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለዘእ መግብዎ ፡ ዘእንበለ ፡ ዳእሙ ፡ ለእመ ፡ እም ጽአ ፡ ስምዐ ፡ ጥዩቀ ። ወለእመ ፡ ነገረ ፡ ዘእመ ገብዎ ፡ ወይቤ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ አስተዋፅአ ፡ ንዋዮ ፡ ላዕሌሁ ፡ እው ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ጠፍአ ፡ በእዴሁ ፡ ዘእንበለ ፡ ተዓውሮ ፡ ቃልኒ ፡ ቃለ ፡ ዚአሁ ። ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ወሀቦ፡ ሎቱ ፡ እምድኅረ ፡ ፀአቱ ፡ እምሕፅኑ ፡ ኢይትወ ከፉ ፡ ቃሎ ፡ ዘእንበለ ፡ በስምዐ ፡ ጥዩቁ ።

፩ሺ.፸፩ ወይደልዎ ፡ ለዘእመገብዎ ፡ ከመ ፡ ያስተዋ ፅእ ፡ ለዘሀሎ ፡ ታሕተ ፡ ምግብናሁ ፡ በከመ ፡ ሥርዓቶሙ ፡ ለእለ ፡ ነበሩ ፡ ከማሁ ፡ ወበሐሳበ ፡ ንዋዩ ፡ ወኢያኅጥእ ፡ ምንተኒ ፡ እምግብረ ፡ መፍቅዳት ፡ በሕይወቱ ፡ ወካቲ ፡ ይእቲ ፡ሲሳይ ወዓራዝ ፡ ወማኅደር ፡ ወእስተዋፅኦ ፡ እምከመ፡ በጽሐ ፡ ጊዜሁ ፡ ወተምህሮ ፡ ግብረ ፡ እድ ፡ ዘተ ቀንዮ ፡ ወዘእእምሮ ። ወከማሁ ፡ ያስተዋፅእ ፡ ዘይትከሀሎ ፡ ላዕሌሁ ፡ ለዘሀሎ ፡ ታሕተ ፡ ምግዚኡ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘይጼንዕ ፡ በከመ ፡ ወልዱ ፡ ወውሉዶ ፡ ውሉዱ ፡ ወብእሲቱ ፡ ወእኀዊሁ ፡ ወእግብርቲሁ ።

፩ሺ.፸፪ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ያመጥብ ፡ መኰንን ፡ ላዕለ ፡ ዘላዕሌሁ ፡ ሊቃሕ ፡ ወኢይትከሀሎ ፡ ከመ ፡ ያስ ተዋፅእ ፡ በንዋዩ ፡ ዘሀሎ ፡ ወከሡትስ ፡ ዕድሜ ፡ ለዘሀሎ ፡ ታሕተ ፡ ምግብ ፡ ዘእንበለ ፡ በምግባ ራት ፡ ዘመፍቅደ ፡ ሕይወት ፡ እስከ ፡ ይፈዲ ፡ ዘተለቅሐ ። ወለእመ ፡ እምነ ፡ ዘተለቅሐ ፡ ሊቃሐ ፡ ካልእ ፡ እንዘ ፡ ሀሎ ፡ ታሕተ ፡ ዝንቱ፡



እንዳች ፡ ገንዘብ ፡ ሊሸጥ ፡ አይገባውም ። በገን ዘቡም ፡ በመነገድ ፡ ወይም ፡ የታወቀ ፡ ነገር ፡ በመያዝ ፡ በዋስ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ በቀጠሮ ፡ (በዱቤ) ፡ በመሸጥ ፡ ሊደፍር ፡ አይገባውም ። ከገንዘቡ ፡ ምንም ፡ እያበድር ። ወደሩቅ ፡ መሄ ድን ፡ ወድዶ ፡ ቢተጋ ፡ (ቢነግ) ፡ በግድ ፡ እደራ፡ ያኖረው ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ፡ እንጂ ። ተበዳሪና ፡ ስእርሱ ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ ያስቀመጡበት ፡ ከተ ስማሙ ፡ እደራ ፡ ከማስቀመጥ ፡ ይልቅ ፡ በዋስ ፡ ወይም ፡ በመያዣ ፡ ለባለጸጋ ፡ ማበደር ፡ ይሻ ላልና ። አደራስ ፡ በሚሰጡት ፡ ሰው ፡ ታማኝ ነት ፡ የሚጠበቅ ፡ ነው ። ለተበዳሪ ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ዋስ ፡ አለውና ። አደራ ፡ ያስጠበቁት ፡ ሰው ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ።

፩ሺ.፸ በመተዳደር ፡ ስር ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ከሹሙ ፡ ጋራ ፡ ቢጣላ ፡ የማስረጃ ፡ ምስክር ፡ ካላመጣ ፡ በቀር ፡ አስተዳዳሪ ፡ እንዳደረጉት ፡ ሰው ፡ ቃል ፡ ይሁን። አስተዳዳሪ ፡ ያደረጉት ፡ ሰው ፡ ገንዘቡን ፡ በእ ርሱ ፡ ላይ ፡ እንዳወጣጣ ፡ ወይም ፡ ያለቸልታ ፡ በእጁ ፡ እንደጠፋ ፡ ቢናገር ፡ ቃሉ ፡ ቃሉ ፡ ነው ። (እርሱ ፡ እንደተናገረው ፡ ይሁን) ። በእርሱ ፡ ስር ፡ ከመተዳደር ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ለእርሱ ፡ ሰጠሁት ፡ ቢል ፡ ያለማስረጃ ፡ ምስክር ፡ ቃሉን ፡ አይቀበሉ ።

፩ሺ.፸፩ አስተዳዳሪ ፡ ላደረጉት ፡ ሰው ፡ በአስተዳደሩ ፡ ስር ፡ ላለው ፡ እንደእርሱ ፡ ሁነው ፡ እንደሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሥርዓትና ፡ እንደገንዘቡ ፡ ሂሣብ ፡ ሊያ ወጣጣ ፡ ይገባዋል ። ለሕይወቱ ፡ ከሚያሻው ፡ ነገር ፡ ምንምን ፡ እያሳጣው ። ይህችም ፡ ምግብ፡ ልብስ ፡ ቤት ፡ አካለ ፡ መጠንም ፡ ካደረሰ ፡ ማጋ ባት ፡ የመገዛትና ፡ የእውቀት ፡ ተግባረ ፡ እድ ፡ መማር ፡ ናት ። እንደዚኸውም ፡ ችግረኛ ፡ ቢሆ ን ፡ በአስተዳደሩ ፡ ስር ፡ ላለው ፡ የተቻለውን ፡ ያወጣጣ ፡ ይኸውም ፡ እንደ ፡ ልጁ ፡ እንደ ፡ ወንዶች ፡ ልጆቹ ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ሚስቱ ፡ እንደወንድሞቹ ፡ እንደባሮቹ ፡ ላሉት ፡ ነው ።

፩ሺ.፸፪ ብድር ፡ ባለበት ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ዳኛ ፡ ሹም ፡ ሊሾም ፡ ይገባል ። ባለ ፡ በገንዘቡ ፡ ሊያወጣጣ ፡ አይቻለውም ። የታወቀ ፡ ቀጠሮስ ፡ ከሕይወት ፡ ፍላጎት ፡ ሥራዎች ፡ በቀር ፡ በመተዳደር ፡ ስር ፡ ላለ ፡ ሰው ፡ የተበደረውን ፡ እስኪከፍል ፡ ድረስ፡ ነው ። የተበደረ ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ በመተዳደር ፡ ስር ፡ ላለ ፡ የሌላውን ፡ ብድር ፡ ቢያምን ፡ በዚያ ፡

ምግብ ፡ ኢይከውን ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ወይእ
ኅዞ ፡ ዕዳሁ ፡ እምድኅረ ፡ ፈድየ ፡ ሊቃሕ ፡ ዘኮነ፡
ታሕተ ፡ ምግብ ፡ በእንቲአሁ ። ወምግብኒ ፡
ይትአተት ፡ በምክንያተ ፡ አእትቶቱ ፡ ዘው
እቱ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘዘሎ ፡ ታሕተ፡ ምግብ ፡
ለባዌ ፡ ወግእምሬ ፡ ወግዑዘ ፡ ያስተብቍዖ ፡
ለመኰንን ፡ ከመ ፡ ያእትት ፡ እምላዕሌሁ ፡ ሥር
ዓተ ፡ እመግቦ ፡ ወስምዐ ፡ ይኩንዎ ፡ ከመ ፡
ውእቱ ፡ ይበቍዕ ፡ ለመግቦ ፡ ምግባራቲሁ ፡
ወንዋዩ ።

፩ሺ.፭፻፫ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ከዊነ ፡ ምግብና ፡ በዐ
ቅሞ ፡ ሰማዕት ፡ ከመ ፡ ይትገኖሥ ፡ እምተኰን
ኖቱ ፡ ለዘአመተበዎ ፡ በላዕሌሁ ፡ ወይቅሙ ፡
ጽሒፈ ፡ ትእዛዝ ፡ በእንተ ፡ ዕድሜሁ ፡ ለምግ
ብና ፡ ወከማሁ ፡ ይደሉ ፡ ዐቅሞተ ፡ ሰማዕት ፡
በእንተ ፡ ተአትቶቱ ፡ ወአግብዖቱ ፡ ገንዘ ፡
ብኑዐ ፡ መኰንን ፡ ከመ ፡ ይጽናዕ ፡ ተሰናእዎ
ቶሙ ፡ ወይጽሐፉ ፡ ትእዛዘ ፡ ለዕድሜ ፡ አእት
ቶቱ ፡ ለምግብና ።

፩ሺ.፭፻፬ ወለእመ ፡ ተገአዘ ፡ ሐፃኒ ፡ ምስለ ፡ መጋቢ ፡
በእንተ ፡ ንዋይ ፡ ይፍትሑ ፡ ማእከሌሆሙ ፡
ለእመ ፡ አጥፍአ ፡ መጋቢ ፡ አው ፡ ሐፃኒ ፡ ዘእ
ንበለ ፡ ዘተሴሰየ ፡ በአእምሮተ ፡ መጋቢ ፡
እመሰ ፡ ጠፍአ ፡ እንበለ ፡ እከይ ፡ አልቦ ፡ ዕዳ ፡
ላዕሌሁ ፡ ወእመሰ ፡ አጥፍአ ፡ ሐፃኒ ፡ ይደሉ ፡
ከመ ፡ ይትዋቀስ ፡ መጋቢ ፡ አምጣነ ፡ ገብረ ።
ወለእመ ፡ ክህለ ፡ ይሴስይ ፡ ሐፃኒ ፡ እምንዋዩ ፡
ወለእመሰ ፡ አልቦ ፡ ይሴስይ ፡ እምንዋይ ፡ ለግ
ብረ ፡ ሕይወቱ ፡ ወእስከ ፡ ይልሀቅ ፡ ዘየሐፅ
ንዎ ። ወዝንቱ ፡ ይደሉ ፡ ለግብረ ፡ ሲሳይ ፡
ወልብስ ፡ ወማኅደር ፡ እስከ ፡ ይበጽሕ ፡ ለአው
ስቦ ፡ ወይትሜሀር ፡ ግብረ ፡ እድ ። ወይደሉ ፡
ሎቱ ፡ ተሴስዮ ፡ ለሐፃኒ ፡ ሠናይ ፡ ሶበ ፡ ኮነ ፡
ፍጹሚ ፡ ፈቃድ ፡ በአምሳለ ፡ ወላዲሁ ፡ ወበአ
ምሳለ ፡ እሙ ፡ ወአኀዊሁ ፡ ወአግብርቲሁ ፡ ወሠ
ያጥ ።

፩ሺ.፭፻፭ ወይደልዎ ፡ ለሐፃኒ ፡ ሠናይ ፡ ይኩን ፡ ጠቢበ ፡
ወየአኀዝ ፡ ንዋዮ ፡ ወዘሐተ ፡ እኂዝሰ ፡ ወምግ
ብና ፡ ኢይደልዎ ፡ ዘእንበለ ፡ መጋቢ ፡ ዘተሠ
ይመ ፡ በዘተሰውቀ ፡ ንዋይ ። ወሐፃኒስ ፡
ይደልዎ ፡ ከመ ፡ የአኀዝ ፡ እምድኅረ ፡ ልህቀ ፡
ዘየሐፅንዎ ፡ ወአጥረየ ፡ ንዋየ ፡ ካልአ ፡ ወከ
ሡተ ፡ በአምጣነ ፡ ሕይወቱ ፡ ለሐፃኒ ፡ ኢይግ



ጊዜ ፡ አይሆንም ። ስለእርሱ ፡ ቍጥጥር ፡ የተደረ
ገበትን ፡ ዕዳ ፡ ከከፈለ ፡ በኋላ ፡ ዕዳ ፡ ይይዘዋል ።
ሹመት ፡ ሊያስወግደው ፡ በሚያበቃ ፡ ምክን
ያት ፡ ይሻራል ። ይኸውም ፡ በመተዳደር ፡ ስር ፡
ያለው ፡ ሰው ፡ አስተዋይ ፡ ዐዋቂ ፡ ራሱን ፡
የቻለ ፡ ቢሆን ፡ ያስተዳደሩን ፡ ሥርዓት ፡ ከእርሱ
ላይ ፡ ያርቅ ፡ ዘንድ ፡ ዳኛውን ፡ ይማልደው ።
ሥራውንና ፡ ገንዘቡን ፡ ለማስተዳደር ፡ እንደ
ሚበቃ ፡ ምስክር ፡ ይሁኑት ።

፩ሺ.፭፻፫ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ከሾሙበት ፡ ሰው ፡ መገዛት ፡
ይርቅ ፡ ዘንድ ። ያስተዳዳሪነት ፡ ሁኔታ ፡ ምስ
ክር ፡ በመጥራት ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ። ስለአስተ
ዳደሩ ፡ ጊዜ ፡ ትእዛዝ ፡ በመጻፍ ፡ ይወስኑ ። እን
ደዚሁም ፡ ስለመሻሩ ፡ (መቅረቱ) ፡ ምስክር ፡
መጥራት ፡ ይገባል ። ስምምነታቸውም ፡
ይጸና ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ በዳኛ ፡ ዘንድ ፡ መግለጽ ፡
ነው ። አስተዳደሩም ፡ ለሚቀርበት ፡ ጊዜ ፡ ትእ
ዛዝ ፡ ይጻፉ ።

፩ሺ.፭፻፬ ሞግዚት ፡ ከመጋቢ ፡ ጋራ ፡ ስለገንዘብ ፡ ቢጣላ ፡
መጋቢ ፡ ወይም ፡ ሞግዚት ፡ አጥፍቶ ፡ እንደ
ሆነ ፡ መጋቢው ፡ ዐውቆት ፡ ከተበላው ፡ በቀር ፡
በመካከላቸው ፡ ይፍረዱ ። ያለ ፡ ክፋት ፡
ቢጠፋ ፡ ግን ፡ ዕዳ ፡ የለበትም ። ሞግዚት ፡ ቢያ
ጠፋ ፡ በሠራው ፡ ልክ ፡ መጋቢ ፡ ሊከራከር ፡
ይገባል ። ሞግዚት ፡ ቢችል ፡ ከገንዘቡ ፡ ይመ
ገብ ፡ ባይኖረው ፡ ግን ፡ የሚያሳድጉት ፡ ሕፃን ፡
እስኪያድግ ፡ ድረስ ፡ ለቁመተ ፡ ሥጋ ፡ ያህል ፡
ከገንዘቡ ፡ ይመገብ ። ይህም ፡ ለማግባት ፡ እስኪ
ደርስ ፡ ተግባረ ፡ እድንም ፡ እስኪማር ፡ ድረስ ፡
ለምግብ ፡ ሥራ ፡ ለልብስ ፡ ለቤት ፡ ሊሆን ፡ ይገ
ባል ። ለመልካም ፡ ሞግዚት ፡ በአባቱና ፡ በናቱ፡
በወንድሞቹና ፡ በደጋጎች ፡ ባሮች ፡ አምሳል ፡
ፈቃድ ፡ ፈጻሚ ፡ ከሆነ ፡ መመገብ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፭፻፭ ለደግ ፡ ሞግዚት ፡ ብልህ ፡ ሊሆን ፡ ገንዘቡንም ፡
ሊይዝ ፡ ይገባዋል ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ቢታወቀው ፡
ገንዘብ ፡ ከተሾመው ፡ መጋቢ ፡ በቀር ፡ መያዝ ፡
ማስተዳደር ፡ አይገባውም ። ሞግዚት ፡ ግን ፡
በሕይወት ፡ ሳለ ፡ የሚያሳድጉት ፡ ልጅ ፡ እስከ ፡
አደገ ፡ የታወቀ ፡ ሌላ ፡ ገንዘብም ፡ እስክ ፡ አገኘ ፡
ድረስ ፡ ሊይዝ ፡ ይገባዋል ። ለቁመተ ፡ ሥጋው ፡

አማን ፡ ዘእንበለ ፡ ለእመ ፡ ኮኑ ፡ ሠያጢ ፡ ወተ
ሣያጢ ፡ ብዉሓነ ፡ ላዕለ ፡ ንዋዮሙ ፡ ወእመ ፡
ኢተሰነአዉ ፡ በአእምሮ ፡ ወዘኢኮኑ ፡ ታሕተ ፡
ምግብና ። ወኢትትፈጸም ፡ ሠይጥ ፡ ወተሣይጦ
ዘእንበለ ፡ በመጥዎ ፡ ሠያጢ ፡ መላኪ ፡ ወተወክ
ፎተ ፡ ተሣያጢ ፡ ዘእንበለ ፡ ትስግልት ። ወክል
ኤሆሙ ፡ ኢይሰነአዉ ፡ ዘእንበለ ፡ ካልእ ፡ ብእሲ
ዘትረይዎ ፡ ለእመ ፡ ኢሐሰበ ። ወለእመ ፡ ሠምረ
፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይኩን ፡ በሥምረተ ፡ ካልኡ ፡
ለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ይፈጽም ፡ ወለእመ ፡ ኢፈቀደ፡
ይሥዐር ። ወለእመ ፡ ተፈልጠ ፡ እምቅድመ ፡
ይሰነአዉ ፡ ላዕለ ፡ ሤጥ ፡ ተፀርዐት ፡ አው ፡ ተወ
ክፎተ ፡ ተማየጢ ፡ ወመጥዎት ፡ ሠያጢ ፡ እስመ
ዘይሠይጥ ፡ ወዘይሣየጥ ፡ ፪ሆሙ ፡ በሥምረ
ቶሙ ፡ ሠእነ ።

፩ሺ፹ ወኢይክሉን ፡ ዘይትፈጸም ፡ ዘስምዐ ፡ ወኢበሥ
ምረት ፡ በሠይጠ ፡ ንዋይ ፡ ዘኢ.ሀለወ ፡ በከዋ
ኒሁ ፡ ወለእመ ፡ ተሰውቀ ፡ ከዋኒሁ ፡ ተፈጸመ ፡
ተሣይጦ ፡ ወእመ ፡ እኮሰ ፡ በሥምረተ ፡ ተሣ
ያጢ ፡ በብሂለ ፡ እሆ ፡ ወእብጥሎ ፡ ወተመጥዎ ፡
በዘያፈልስዎ ፡ ከመ ፡ ይፍልስ ፡ ለእመ ፡ ፈለሰ ፡
ተሠያጢ ፡ በእፍልስቶ ፡ ዘተሣየጦ ፡ እመከኑ ፡
አው ፡ በተአምኖቱ ፡ ከመ ፡ ያፍልስ ፡ ኀበ ፡
ምልክናሁ ፡ ዘከመ ፡ እንስሳ ፡ ወእግብርት ፡
ወእለ ፡ ይትበልዑ ፡ ዘበበያታሆሙ ፡ ወእለ ፡
ይስትዩ ፡ ኪያሆሙ ፡ ወእለሂ ፡ ይለብስዎሙ ።
ወሰፀፀሁ ፡ ወመሠግብታት ፡ ወዘይትሜጠ
ውዎ ፡ በእደ ፡ ተመጥዎ ፡ በሰንቄ ፡ ባሕርይ ፡
ወዘእንዘብዎሂ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ለዝንቱ ፡
እምነ ፡ ሥርጋዌ ፡ ወይትአመኑ ፡ ወይቆቶ ፡
እእምሮቶሙ ፡ ባቲ ፡ ዘከመ ፡ እፅፃድ ፡ ወግን
ዛት ፡ ወምድር ።

፩ሺ፹፩ ወተሣይጦስ ፡ ወሢጠ ፡ ቦ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘይክ
ውን ፡ በጽሒፍ ፡ ወቦ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘእንበለ ፡
ጽሒፍ ። ወዘሂ ፡ ይከውን ፡ በጽሒፍ ፡ ፍጻሜ ፡
ሁኒ ፡ ከመ ፡ የሀሉ ፡ በእደ ፡ ተሣያጢ ፡ መጽሐፍ
ዘውስቴቱ ፡ ስምዐ ፡ ፪ቱ ፡ ስማዕት ፡ አው ፡ ፫ቱ
እው ፡ ዘይበዝኁ ፡ እመኒ ፡ በጽሒፈተ ፡ ፩ዱ ፡
እምስማዕታት ፡ አው ፡ በጽሒፈተ ፡ ሠያጢ ፡
አው ፡ በጽሒፈተ ፡ ጸሓፊ ፡ ዘይትሌዎ ፡ ጽሕ
ፈተ ፡ ሢጥ ። ወዘይነግር ፡ መጽሐፉ ፡ ተሰናእ
ዎተ ፡ ሢጥ ፡ ወውስንያቲሃ ፡ ወከዋኔ ፡ ንዋይ ፡
ዘይሠየጥዎ ፡ ወመጠነ ፡ ሢጡ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡

ዘባቸው ፡ ሥልጣን ፡ ያላቸው ፡ ካልሆኑ ፡
በቀር ፡ መገበያየት ፡ እውነተኛ ፡ አትሆንም ።
በዕውቀት ፡ ካልተስማሙ ፡ ከመተዳደር ፡ ሥር፡
ካልሆኑ ፡ ገዥ ፡ ለሻጭ ፡ በመስጠት ፡ ገዥም ፡
ያለቅሚያ ፡ በመቀበል ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡
መሸጥ ፡ መግዛት ፡ አትፈጸምም ። የመረ
ጡት ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ካልተቆጣጠረ ፡ ሁለቱ ፡
አይስማሙም ። ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ በአንደኛው ፡
ፈቃድ ፡ እንዲሆን ፡ ከወደደ ፡ ቢወድ ፡ ይፈጽም
ባይወድ ፡ ይሻር ። ከመስማማታቸው ፡ በፊት ፡
በዋጋ ፡ ቢለያዩ ፡ ትቀራለች ። ወይም ፡ የገዥ ፡
መቀበልና ፡ የሻጭ ፡ መስጠት ፡ የሚሸጥና ፡
የሚገዛ ፡ ሁለቱ ፡ በፈቃዳቸው ፡ ነውና ።

፩ሺ፹ በጨረታው ፡ የሌለ ፡ ገንዘብን ፡ በመሸጥ ፡
ጊዜ ፡ በምስክርና ፡ በመውደድ ፡ የሚፈጸም ፡
አይሆንም ። ጨረታው ፡ ከታወቀ ፡ መሸሸጥ ፡
ተፈጸመ ። ያለዚያ ፡ ግን ፡ እሺ ፡ ወይም ፡ እንቢ ፡
ቢል ፡ በገዥ ፡ ፈቃድ ፡ ነው ። የገዛውን ፡ ከቦ
ታው ፡ በማዛወር ፡ ወይም ፡ ወይማዛቱ ፡ (እጅ
ንቱ) ፡ ያዛውረው ፡ ዘንድ ፡ በመተማመኑ ፡ ገዥ፡
ከቦታው ፡ ቢዛወር ፡ ይዛወር ፡ ዘንድ ፡ በሚመስ
ዱት ፡ ገንዘብ ፡ መቀበል ፡ ነው ፡ ይኸውም ፡
እንደ ፡ እንስሳ ፡ እንደ ፡ ባሮች ፡ በየወገናቸው ፡
እንደሚበሉና ፡ እንደሚጠጡ ፡ እንደሚለብሱ
ቸው ፡ እንደእንጨቶች ፡ እንደማጥኖች ፡ መቀ
በልን ፡ በእጅ ፡ እንደሚቀበሉት ፡ እንደሰንቆና፡
እንደእንጠሩትም ፡ ከነጥ ፡ ወገን ፡ ይህን ፡ እንደ
መሰለው ፡ ያለ ፡ ነው ። እርሷንም ፡ አውቀው ፡
መረዳትን ፡ ይመኑ ። ይኸውም ፡ እንደቦታ ፡
እንደ ፡ ተክል ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ ያለ ፡ ነው ።

፩ሺ፹፩ መግዛትና ፡ መሸጥ ፡ ከእነርሱ ፡ ወገን ፡ በጽሕ
ፈት ፡ የሚሆን ፡ አለ ። ከእነርሱም ፡ ወገን ፡ ያለ
ጽሕፈት ፡ የሚሆን ፡ አለ ። በጽሑፍ ፡ የሚሆ
ነው ፡ መጨረሻው ፡ በውስጡ ፡ ሁለት ፡ ወይም፡
ሦስት ፡ ወይም ፡ የሚበዙ ፡ ምስክሮች ፡ ያሉት ፡
ደብዳቤ ፡ በገዢ ፡ እጅ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
ከምስክሮቹ ፡ አንዱ ፡ በጻፈውም ፡ ቢሆን ፡
ወይም ፡ ሻጭ ፡ በጻፈው ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ዋጋን
መጻፍ ፡ የሚገባው ፡ ጸሓፊ ፡ ቢጽፈው ።
መጽሐፉም ፡ የሚናገር ፡ የዋጋውን ፡ ስምም
ነትና ፡ ውስኗን ፡ የሚሸጡትን ፡ ገንዘብ ፡

ለሐኒፆታ ፡ ዘተሣየጠ ፡ ወዝንቱኒ ፡ ወዘእ ምስሊሁ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ተዐውቀ ፡ ኀበ ፡ ሰብእ ። ወሁቀትሰ ፡ ዘይሰነእዋ ፡ ላዕሌሁ ፡ በሤጥ ፡ ይጸንዕ ፡ ወለእመ ፡ ተሠይጠ ፡ ተክል ፡ ወሀሎ ፡ ፍሬ ፡ በዘሣጠ ፡ ኢያገብርዎ ፡ ለተሣ ያጢ ፡ አፍልሶቶ ፡ ወኢይክልእዎ ፡ ወሰቅዮቶ ፡ ወተሰናእዎተ ፡ ሀልዎቱ ፡ ወሰቅዮቱ ። እው ፡ እፍልሶቱ ፡ ይጸንዕ ። ወለዘሂ ፡ ይሰፍርዎ ፡ ወይሜጥንዎ ፡ ወይደልዎ ፡ በመዳልው ፡ ይደሉ ፡ ሤጡ ፡ ወተሣይጦቱ ፡ ግሁደ ፡ ወመ ዳልዉኒ ፡ ወዘይትሜጠን ፡ በእመት ፡ ወዘ ይሰፈርሃ ፡ ይኀድሶ ።

፩ሺ፹፯ ወእመቦ ፡ ዘተሣየጠ ፡ ልብሰ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እመት፡ በ፩ዱ ፡ ድርኅም ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይሣየጥ ፡ ኵለንታሁ ፡ እው ፡ ዘፈቀደ ፡ እምኔሁ ፡ በመ ጠነ ፡ ውእቱ ፡ ሤጥ ። ወእመኒ ፡ ተሣየጠ ፡ ወኮነ ፡ እምጣኒሃ ፡ ፲ተ ፡ በእመት ፡ ይሣየጥ ፡ በ፲ት ፡ ድርኅም ። ወእመኒ ፡ ኮነት ፡ ዘተሐጽጽ፡ ድልው ፡ ሎቱ ፡ ሥምረት ፡ ወለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ይንሣእ ፡ ኪያሃ ፡ በሐሳበ ፡ ሤጡ ፡ ለእመ ፡ ሠምረ ፡ ሠያጢ ፡ ወለእመ ፡ ኢፈቀደ ፡ ይሠ ዐር ፡ ተሣይጦ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘይበዝኅ ፡ ይኩን ፡ በሥምረተ ፡ ፪ሆሙ ፡ በእንተ ፡ ዘፈድ ፈደ ፡ እምዓት ፡ ባሕቲቱ ።

፩ሺ፹፰ ወእመቦ ፡ ዘርእየ ፡ ምንተኒ ፡ እምንዋዩ ፡ እንዘ ፡ ይሠይጥዎ ፡ በእደ ፡ ካልኡ ፡ ወተከሀሎ ፡ ከመ ፡ ይክልእ ፡ ወኢተናገረ ፡ ይኩኑን ፡ ዘከመ ፡ ለሊሁ ሤጠ ፡ ወይደልዎ ፡ ለገብሩኒ ፡ ከመ ፡ ይሣየጥ ፡ ወዘተሣየጠሂ ፡ ይኩን ፡ ለእግዚኡ ።

፩ሺ፹፱ ምዕራፍ ፡ ዳግማዊ ፡ ወለእመ ፡ ማስነ ፡ ዘተሠ ይጠ ፡ እምቅድመ ፡ ፍጻሜ ፡ ሠይጥ ፡ እመኒ ፡ ውስተ ፡ እዴሁ ፡ ለዘተሣየጠ ፡ ወእመኒ ፡ እ.ዘ ለወ ፡ እመ ፡ ኮነ ፡ ተሣያጢ ፡ ዘአማስኖ ፡ ይኩን፡ ሎቱ ፡ ወይእኅዞ ፡ ዕዳ ፡ ወይደልዎ ፡ ለሠያጢ ፡ ሤጡ ፡ በከመ ፡ ተሰነእዉ ፡ ቅድመ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ካልእ ፡ ዘአማስኖ ፡ ይፍዲ ፡ በየንቲሁ ፡ ወይኅረይ ፡ ተሣያጢ ፡ እመኒ ፡ ለአብጥሎ ፡ ወእመኒ ፡ ለአቅሞ ፡ ወሠያጢሂ ፡ ይትኀ ሠሦ ፡ ለዘአማስኖ ፡ በመጠነ ፡ ሤጡ ። ወለ እመ ፡ ጠፍአ ፡ እምድኅረ ፡ ፍጻሜ ፡ ተሣ ይጦ ፡ እመኒ ፡ ኵለንታሁ ፡ እው ፡ መንፈቁ ፡ ይኩን ፡ ለዘተሣየጦ ፡ ወየሀብ ፡ መጠነ ፡ ሤጡ ፡ ለሠያጢ ፡ ወእመኒ ፡ ማስነ ፡ በዕለተ ፡ ተሣይጦ ።



የገዛ ፡ ሊሠራበት ፡ ይግባ ። ይህን ፡ የመሰለውም በሰው ፡ ዘንድ ፡ እንደታወቀው ፡ ይሁን ። የተስ ማሙበት ፡ ዕውቀትስ ፡ በዋጋ ፡ ይጸናል ። ተክል ቢሸጥ ፡ በተሸጠው ፡ ተክል ፡ ፍሬ ፡ ቢኖርበት ፡ እንዲነቅለው ፡ ገዢውን ፡ እያስገድዱት ። ውሃ ፡ ከማጠጣት ፡ አይከልክሉት ። የመኖ ሩና ፡ ውሃ ፡ የማጠጣቱ ፡ ወይም ፡ ነቅሎ ፡ የመሄዱ ፡ መስማማት ፡ ይጸናል ። የሚሰፍሩ ትንና ፡ የሚለኩትን ፡ በሚዛን ፡ የሚመዝኑ ትንም ፡ በግልጽ ፡ መሸጥና ፡ መግዛት ፡ ይገ ባል ። የሚመዘነውና ፡ በክንድ ፡ የሚለካው ፡ የሚሠፈረውም ፡ ይሻላል ።

፩ሺ፹፯ እያንዳንዱን ፡ ክንድ ፡ ልብስ ፡ በአንድ ፡ ድኀር ም ፡ የገዛ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ሁሉንም ፡ ወይም ፡ በዚያ ፡ ዋጋ ፡ ልክ ፡ ከእርሱ ፡ የወደደውን ፡ ሊገዛ ፡ ይገባዋል ። ቢገዛትም ፡ ልኳ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ ቢሆን ፡ በመቶ ፡ ድሪም ፡ ይግዛት ። ያነ ሰች ፡ ብትሆንም ፡ ለእርሱ ፡ ፈቃድ ፡ ይገባዋል። በዋጋው ፡ ሂሳብ ፡ እርሷን ፡ ሊወስድ ፡ ቢወድ ፡ ባይወድም ፡ መግዛቱ ፡ ይቀራል ። የሚበዛ ፡ ቢሆን ፡ ከመቶ ፡ ስለሚበዛ ፡ ብቻ ፡ በሁለቱ ፡ ፈቃድ ፡ ይሁን ።

፩ሺ፹፰ ከገንዘቡ ፡ እንዳች ፡ በሌላው ፡ እጅ ፡ ሲሸጡት ፡ ያየ ፡ ቢኖር ፡ ሊከለክል ፡ ሲቻለው ፡ ባይናገር ፡ እርሱ ፡ እንደሸጠው ፡ ይሆናል ። ባሪያ ፡ ሊገበ ያይ ፡ ይገባዋል ። የገዛውም ፡ ለጌታው ፡ ይሁን ።

፩ሺ፹፱ ሁለተኛው ፡ ምዕራፍ ፡ ከመሸጥ ፡ ፍጻሜ ፡ አስ ቀድሞ ፡ የተገዛው ፡ ቢጠፋ ፡ በገዢ ፡ እጅ ፡ ቢኖ ርም ፡ ባይኖርም ፡ ያጠፋው ፡ ገዢው ፡ ከሆነ ፡ በእርሱ ፡ ይሁን ። ዕዳም ፡ ይይዘዋል ፡ አስቀ ድሞ ፡ እንደተስማሙ ፡ ዋጋው ፡ ለሻጭ ፡ ይገ ባዋል ። ያጠፋው ፡ ሌላ ፡ ቢሆን ፡ ስለእርሱ ፡ ፈንታ ፡ ይከፈል ። ለመወሰንም ፡ ቢሆን ፡ ለማ ፍረስም ፡ ቢሆን ፡ ገዢ ፡ ይምረጥ ። ሻጭም ፡ በዋጋው ፡ ልክ ፡ እጥፊውን ፡ ይፈላለገው ። ከግዢ ፡ ፍጻሜ ፡ በኋላ ፡ ቢጠፋ ፡ መላውም ፡ ቢሆን ፡ ግማሹም ፡ ቢሆን ፡ ለገዢው ፡ ይሁን ። በገዛበት ፡ ቀን ፡ ቢጠፋም ፡ የዋጋውን ፡ ልክ ፡ ለሻጭ ፡ ይስጥ ።

አንቀጽ ፡ ፴፫ ።

፩ሺ.፻፱ ወእመ ፡ ኮነ ፡ ሥዩጥ ፡ ገብረ ፡ ወማስነ ፡ ምንትኒ ፡ እምአባላቲሁ ፡ እመኒ ፡ እግሩ ፡ አው ፡ እዴ ፡ አው ፡ ዓይኑ ። ወእመኒ ፡ ኮነ ፡ ማኅደረ ፡ ወውዕየ ፡ ዘተሰንታሁ ፡ አው ፡ መንፈቁ ፡ ወእመኒ ፡ ኮነት ፡ ሀገረ ፡ ወኀለፈ ፡ ፈለግ ፡ ላዕሌሃ ፡ በዘተሰንታሃ ፡ አው ፡ ኀበ ፡ ፩ዱ ፡ መካን፡ እምኔሃ ፡ ወማስነት ፡ አው ፡ ውሕደት ፡ አው ፡ ወድቀ ፡ አብያቲሃ ፡ አው ፡ አእዋሚሃ ፡ ወዘኩሉ ፡ ዘይከውን ፡ ዘከመ ፡ ዝንቱ ፡ እንዘ ፡ ኢይትዐወቅ ፡ ምንትኒ ፡ ጉሕሉት ፡ በላዕለ ፡ ሠያጢ ፡ ሀብት ፡ ዚአሁ ፡ ውእቱ ፡ ለተሣያጢ ፡ ወይከውን ፡ ሠያጢ ፡ ድኁነ ፡ እምሰዳ ። ወከማሁ ፡ ዘኩሉ ፡ ዘተወስከ ፡ ውስተ ፡ ግብር ፡ ሥዩጥ ፡ እምንዋይ ፡ ዘይሠይጥዎ ፡ በክዋኔ ፡ ወበሜጥ ፡ ይከውን ፡ ለተሣያጢ ፡ ህየንተ ፡ ሠያጢ ። ወለእመ፡ ተገአዘ ፡ በእንተ ፡ አብጥሎቱ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለሠያጢ ፡ ምስለ ፡ መሐላሁ ። ወእመኒ ፡ በውሳኔ ፡ ይኩን፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለተሣያጢ ፡ ምስለ ፡ መሐላሁ ። እስከ ፡ ያመጽእ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ በጥያቄ ፡ ሰማዕት ፡ ወይፈትሑ ፡ ፍትሐ ፡ ዘእሆሙ ።

፩ሺ.፲ ምስራፍ ፡ ማልስ ፡ ወሠያጢ ፡ ለእመ ፡ ነረየ ፡ ይሣጥ ፡ ሎቱ ፡ ንዋየ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ሣጥኩ ፡ እነ ፡ እገሌ ፡ በጊዜሁ ፡ ለእገሌ ፡ በሣጠ ፡ እገሌ ፡ ወፍጻሜሁኒ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ሥምረቱ ፡ ለሠያጢ ፡ ወመማበቱ ፡ በሥምረተ ፡ ተሣያጢ ፡ እስከ ፡ ይፈትዎ ፡ የሀበ ፡ ዕድሜ ፡ መጠነ ፡ ፫ቱ ፡ ሰሌታት ፡ አው ፡ ዘይበዝኅ ፡ በዘ ኢይማስን ፡ ፍጡነ ። ወንዋይኒ ፡ ዘተሠይጠ ፡ የሀሉ ፡ በምልክናሁ ፡ ለሠያጢ ፡ በዕድሜ ፡ ነርየት ፡ ወኢይደልዎ ፡ ይሥራዕ ፡ ውስቴቱ ፡ ዘእንበለ ፡ መባሕት ፡ ተሣያጢ ። ወለእመ ፡ አስተባውሐ ፡ ወኢከልአ ፡ እምአስተዋዕአቱ ፡ ተፈጸመ ነርየት ፡ ሠያጢ ፡ ወይለዎ ፡ ሣጡ ። ወለእመ ፡ ሞተ ፡ ዘቦቱ ፡ ኅርየት ፡ ተሥዕረት ፡ ተሣያጢ ።

፩ሺ.፲፩ ወዘሂ ፡ ተሣየጠ ፡ ምንተኒ ፡ ዘከመ ፡ ሎቱ ፡ ግብር ፡ እሙር ፡ ወኢተረከበ ፡ ቦቱ ፡ ዘከመ ፡ ተሣየጠ ፡ ገብረ ፡ ዘከመ ፡ ውእቱ ፡ ኬንያ ፡ ወኢረከበ ፡ ከማሁ ፡ ይኩን ፡ በኅርየቱ ፡ ለተሣያጢ ፡ ለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ይንሥእ ፡ ወእመ ፡ ኢፈቀደ ፡ ይሚጦ ። ወከማሁ ፡ ለእመ ፡ ተሣየጠ ፡ ምንተኒ ፡ ዘኢርእዮ ፡ ውእቱ ፡ አው ፡ መጋቢሁ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ኅረየ ። ወለእመ ፡

ስለ ፡ መሸጥና ፡ መግዛት ።

፩ሺ.፻፱ የተሸጠው ፡ ባሪያ ፡ ቢሆን ፡ ከሕዋሳቶቹ ፡ እግሩም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ እጁ ፡ ወይም ፡ ዐይኑ ፡ አንዳች ፡ ቢጎድል ፡ ቤትም ፡ ቢሆንና ፡ ግማሹ ፡ ወይም ፡ እኩሌታው ፡ ቢቃጠል ፡ መንደር ፡ ብትሆን ፡ ጎርፍ ፡ በእርሷ ፡ ላይ ፡ በመላዋ ፡ ወይም ፡ በእርሷ ፡ በአንዱ ፡ ቦታ ፡ በኩል ፡ ቢሄድባት ፡ ብትናድ ፡ ወይም ፡ ብትጐደጐድ ፡ ወይም ፡ ቤቶቿ ፡ ወይም ፡ ዛፎቿ ፡ ቢወድቁ ፡ በሻጭ ፡ ምንምን ፡ ተንኮል ፡ ሳይታወቅ ፡ እንደዚህ ፡ የሚሆነው ፡ ሁሉ ፡ ለገዢ ፡ ገንዘቡ ፡ ነው ። ሻጩም ፡ ከሰዳ ፡ የዳነ ፡ ይሆናል ። እንደዚኸውም ፡ በጨዋታረታውና ፡ በዋጋው ፡ ከሚሸጡት ፡ ገንዘብ ፡ በሚሸጥ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ የተጨመረው ፡ ሁሉ ፡ ስለሻጭው ፡ ፈንታ ፡ ለገዢ ፡ ይሆናል ። ስለማፍረስ ፡ ቢከራከሩ ፡ ከመሐላው፡ ጋር ፡ እንደሻጭ ፡ ቃል ፡ ይሁን ። በጭማሪም ፡ ቢሆን ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ በእርግጥ ፡ ምስክሮች ፡ እስኪያመጣ ፡ ድረስና ፡ ፍርዳቸውን ፡ እስኪፈርዱላቸው ፡ ድረስ ፡ ከመሐላው ፡ ጋር ፡ እንደገዥ ፡ ቃል ፡ ይሁን ።

፩ሺ.፲ ሦስተኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ሻጭ ፡ እኔ ፡ እገሌ ፡ በእገሌ ፡ ጊዜ ፡ በእገሌ ፡ ዋጋ ፡ ሸጥሁ ፡ ብሎ ፡ ሊሸጥለት ፡ ቢወድ ፡ ፍጻሜውም ፡ የሻጭ ፡ ፈቃድ ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ መመለሱም ፡ በገዢ ፡ ፈቃድ ፡ ፈጥኖ ፡ በማይጠፋ ፡ ገንዘብ ፡ እስኪፈትነው ፡ ድረስ ፡ ፫ ፡ ቀናት ፡ ያህል ፡ ወይም ፡ የሚበዛ ፡ ቀጠሮ ፡ ይስጠው ። የሸጠው ፡ ገንዘብም ፡ በምርጫው ፡ ቀጠሮ ፡ በሻጭ ፡ እጅነት ፡ ይኑር ። ያለገዢ ፡ ፈቃድ ፡ በገንዘቡ ፡ ሊሠራበት ፡ አይገባውም ። ከፈቀደ ፡ ካልከለከለውም ፡ የሻጭ ፡ ምርጫ ፡ ተፈጸመ ። ዋጋውም ፡ ተገባው ። ምርጫ ፡ ያለበት ፡ ቢሞት ፡ ግን ፡ ሺያጭ ፡ ይቀራል ።

፩ሺ.፲፩ ምንም ፡ የገዛ ፡ ሰው ፡ ይኸውም ፡ የታወቀ ፡ ሥራ ፡ እንዳለው ፡ ያለ ፡ ነው ። ባይገኝበትም ፡ ይኸውም ፡ ብልሀ ፡ ነው ፡ የተባለ ፡ ባሪያን ፡ እንደገዛ ፡ ያለ ፡ ነው ፡ እንደተባለውም ፡ ባያገኘው ፡ ገዢ ፡ እንደ ፡ መረጠው ፡ ይሁን ፡ ቢወድ ይውሰደው ። ባይወድ ፡ ይመልሰው ፡ እንደዚሁም ፡ እርሱ ፡ ወይም ፡ መጋቢው ፡ ያላየውን ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ ቢገዛ ፡ እንደመረጠ ፡ ይሁን ።

እንቀጽ ፡ ፵፫ ።

፩ሺ.፩፻፲፪ ወሢመተ ፡ ፈታሒስ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ በፍጽሜ ፡ ሕግ ፡ ወፍጥረት ። ወዘይቀድምስ ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ በአሪት፡ ውስተ ፡ መጽሐፍ ፡ ኃምስ ፡ ሢሙ ፡ ለክሙ ፡ ፈታሕተ ፡ በኵሉ ፡ አህጉሪክሙ ፡ እንተ ፡ ይሁበክሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክክሙ ፡ ከመ ፡ ይፍትሑ ፡ ማእከለ ፡ ሰብእ ፡ ፍትሐ ፡ ርቱዐ ፡ ዘኢያጸንን ፡ በጊዜ ፡ ፍትሕ ፡ ወኢይነሥኡ ፡ ገጸ ወኢሕልያነ ፡ እስመ ፡ ሕልያን ፡ ያዐውር ፡ አዕይንተ ፡ ጠቢባን ፡ ከመ ፡ ኢይርአዩ ፡ ጽድቀ ፡ ወይዌልጥ ፡ ቃለ ፡ ርቱዐ ።

፩ሺ.፩፻፲፫ ወዳግማዊኒ ፡ እስመ ፡ ተጋብአ ፡ ህገራዊ ፡ ኢይትኀደግ ፡ ዘእንበለ ፡ ትኩን ፡ ተጋእዞ ፡ በቱ ፡ እምነ ፡ ግብረት ፡ ወኢይትፌጸምኬ ፡ በሠናይ ፡ ዘእንበለ ፡ ፈታሒ ፡ ዘይፈትሕ ፡ ማእከለ ፡ ተጋአዝያን ፡ ለጽኑዕ ፡ ወለድኩም ፡ ለለባዊ ፡ ወለዐብድ ፡ በከመ ፡ ይደሉ ፡ ለገቢረ ፡ ርትዕ ።

፩ሺ.፩፻፲፬ ወዘሂ ፡ ጸነ ፡ እምትእዛዘ ፡ ፈታሒ ፡ ይኤምር ፡ ካዕበ ፡ ከመ ፡ ይደሉ ፡ አቅሞቱ ፡ ወሥርዓተ ፡ አቅሞቱኒ ፡ ናሁ ፡ ይነብር ፡ እምትእዛዘ ፡ ፍትሕ ። ወይመርሕ ፡ ካዕበ ፡ ኀበ ፡ ይሌወ ፡ ሢመት ፡ እስመ ፡ ትእዛዘ ፡ ሢመትኒ ፡ ናሁ ፡ ቀዳሚ ፡ ተነግሮ ፡ በቀኖናት ፡ እምትእዛዘ ፡ ሢመት ፡ ዘክህናት ፡ ወሊቃነ ፡ ክህናት ፡ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ነእዝዝ ፡ በዝየኒ ፡ ትእዛዘ ፡ ሢመተ ፡ ፍትሕ ፡ እምኀበ ፡ ውእቱ ፡ ፈታሒ ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ይከውን ፡ ሢመቱ ፡ ሠናየ ፡ ወትቀውም ፡ ፍትሐ ፡ ዚእሁ ። ወኍልቈሆን ፡ ፲ወ፫ቱ ፡ ትእዛዛት ።

፩ሺ.፩፻፲፭ ቀዳሚሆን ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ብእሲ ፡ ወዝንቱ ፡ ዘያስተጋብእ ፡ አብጽሖተ ፡ መጠን ፡ ዘብእሲ ፡ ወብጽሖትስ ፡ ብጹሐ ፡ እምዓመ ፡ ዘፈጸመ ፡ ሕገ ፡ ውርዛዌ ። ወዘእንበሌሁሰ ፡ ኢይትፌጸም ፡ ልቡና ፡ ወኢይበቍዕ ፡ ለሢመት ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ማእከለ ፡ ዐቢያን ፡ ወልኁቃን ፡ ወዘይመስሎሙ ፡ ወኢይሤኒ ፡ ከመ ፡ የሀልዉ ፡ ዘአምሳለ ፡ እሉ ፡ ቅድሜሁ ፡ ለዘኢበጽሐ ፡ ኀበ ፡ መጠን ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ሎሙ ። ወበላዕሌሆሙ ፡ ሎሙ ፡ ብሂል ፡ ለእለ ፡ ይመውዑ ፡ ወበላዕሌሆሙ፡ሎሙ ፡ ብሂል፡ለእለ ፡ ይትመወዑ ።

፩ሺ.፩፻፲፮ ወበእንተ ፡ ተባዕትኒ ፡ እስመ ፡ ብእሲ ፡ ርእሳ ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

፩ሺ.፩፻፲፪ የዳኛ ፡ መሾምስ ፡ በሕግና ፡ በፍጥረት ፡ ፍጹም የተገባ ፡ ነው ። የሚቀድመው ፡ ግን ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ በኦሪት ፡ በአምስተኛው ፡ መጽሐፍ ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚሰጣችሁ ፡ አገሮቻችሁ ፡ ሁሉ ፡ በሰዎች ፡ መካከል ፡ የቀና ፡ ፍርድ ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ፡ ለራሳችሁ ፡ ዳኞችን ፡ ሹሙ ። በፍርድ ፡ ጊዜ ፡ የማያደሉ ፡ ፊት ፡ አይተው ፡ መማለጃ ፡ (ጉቦ) ፡ የማይቀበሉ ፡ መማለጃ ፡ (ጉቦ) ፡ እውነትን ፡ እንዳያዩ ፡ የብልሆችን ፡ ዓይን ፡ ያሳውራልና ። የቀናውንም ፡ ፍርድ ፡ ይለውጣልና ፡ ብሎ ፡ እንደተናገረ ። (ዘዳግ ፡ ፲፮ ፡ ፲፰ - ፳) ።

፩ሺ.፩፻፲፫ ሁለተኛውም ፡ በህገር ፡ የምትደረግ ፡ ስብሰባ ፡ ከሥራ ፡ ወገን ፡ ክርክር ፡ ሳይሆንባት ፡ አትፈታምና ። በተጣሉት ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ ለብርቱና ለደካማ ፡ ለዐዋቂና ፡ ላለዐዋቂም ፡ ቅን ፡ ለመሥራት ፡ እንደሚገባ ፡ የሚፈርድ ፡ ዳኛ ፡ ከሌለ፡ በመልካም ፡ አይፈጸምምና ።

፩ሺ.፩፻፲፬ ከዳኛ ፡ ትእዛዝ ፡ የጸነነውንም ፡ (የተሰወረውንም) ፡ ሁለተኛ ፡ መቅጠር ፡ እንደሚገባ ፡ ያመለክታል ። የቀጠሮው ፡ ሥርዓትም ፡ ከፍርድ ፡ ትእዛዝ ፡ የተነሣ ፡ እነሆ ፡ ይወሰናል ። ዳግመኛም ፡ ለሹመት ፡ ወደመገባት ፡ ይመራል ። እነሆ ፡ የሹመት ፡ ትእዛዝ ፡ ከካህናትና ፡ ከሊቃነ ፡ ካህናት ፡ ሹመት ፡ ትእዛዝ ፡ የተነሣ ፡ አስቀድሞ ፡ በመጻሕፍት ፡ ተነግሯልና ፡ በዚህም ፡ ሹመቱ ፡ መልካም ፡ የምትሆንበትንና ፡ ፍርዱ ፡ የምትጸናበትን ፡ የፍርድ ፡ ትእዛዝ ፡ ከዚህ ፡ ዳኛ ፡ ዘንድ ፡ ልናዝዝ ፡ ይገባል ። ቁጥራቸውም ፡ ፲፫ ፡ ትእዛዛት ፡ ናቸው ።

፩ሺ.፩፻፲፭ መጀመሪያቸው ፡ ወንድ ፡ እንዲሆን ፡ ነው ። ይህም ፡ የወንድ ፡ አካለ ፡ መጠን ፡ መድረስን ፡ የፈጸመ ፡ ነው ። አካለ ፡ መጠን ፡ ማድረስም ፡ የጉልምስናን ፡ ሕግ ፡ የፈጸመ ፡ ነው ። ያለዚያስ ፡ አእምሮ ፡ አይደላደልም ። በታላላቆችና ፡ በሽማግሌዎች ፡ በመሰሎቻቸውም ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ፡ ለሹመት ፡ አይበቃም ። እነዚህን ፡ የመሰሉ ፡ ሰዎች ፡ አካለ ፡ መጠን ፡ ባላደረሰው ፡ ዳኛ ፡ ፊት ፡ ይፈርድላቸው ፡ ዘንድ ፡ ሊቆሙ ፡ አይገባም ። በሚረቱት ፡ ላይ ፡ ነገር ፡ አለ ። በሚረቱት ፡ ላይም ፡ ነገር ፡ አለ ።

፩ሺ.፩፻፲፮ ስለ ፡ ወንዶችም ፡ ወንድ ፡ ለሴት ፡ ገዥዋ ፡

ለብእሲት ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ ሐዋርያ ፡ ወፍትሕኒ፡ ይደሉ ፡ ለርእሰ ፡ እምታሕቴሆሙ ፡ እስመ ፡ ብእሲ፡ ክቡድ ፡ ልቡና ፡ ውእቱ ፡ ወሎቱ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ ውስተ ፡ ቀኖናት ፡ ከመ ፡ ብእሲት ፡ ኢትምሀር ፡ ወኢትኩን ፡ እምኍልቈ ፡ ካህናት ፡ ወፈታሒኒ ፡ ኢይኩን ፡ ዘእንበለ ፡ ካህን ።

፩ሺ.፱፻፲፯ ወዳግማዊ ፡ ልብ ፡ ምስለ ፡ አእምሮታቲሁ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ጠባይዕ ፡ እንስሳዊ ፡ ወካልእ ኒ ፡ ረባኒዊ ፡ ወአልቦ ፡ ዘይበቍዕ ፡ እንዘ ፡ የኀልዮ ፡ ወኢየአክሎ ፡ ውስቴቱ ፡ በዘይሰቀል ፡ በአንብሮ ፡ ወውእቱ ፡ ከዊነ ፡ ተላዌ ፡ ለረኪበ ፡ ጸሕቀት ፡ አላ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘይፈሊጥ ፡ ፍልጠተ ፡ አበይት ፡ ወመናየ ፡ አእምሮ ፡ ርትዕ ፡ ዐሪት ፡ ዘይበጽሕ ፡ በትሩፋት ፡ ልቡናሁ ፡ ኀበ ፡ ከሚተ ፡ ፍትሕ ፡ ዘንጹሕ ፡ ወፍጻሜ ፡ ዘተኀብአ ፡ እስመ ፡ በከመዝ ፡ ውእቱ ፡ ይፈትሕ ፡ ማእከለ ፡ ማእምራን ፡ ወእኩያን ። ወኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘየሐጽጽ ፡ እምኔሆሙ ፡ ልበ ፡ ወኢ ፡ ዘይወኑድ ፡ አእምሮ ።

፩ሺ.፱፻፲፰ ሣልስ ፡ ይኩን ፡ ምእመነ ፡ ኦርቶዶክሳዌ ፡ ወካህነ ፡ በጥዩቅ ።

፩ሺ.፱፻፲፱ ራብዕ ፡ ገቢረ ፡ ርትዕ ፡ ዘይደሉ ፡ ለፈታሕያን፡ ወለሰማዕት ፡ ወቀዳማዊሰ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ምእመነ ፡ ወጠቢበ ፡ ዘርኁቀ ፡ እምንቅፈት ፡ ወድኁነ ፡ እምነውር ፡ ሀዲአ ፡ ለምሕረት ፡ ወለሥምረት ፡ ተዐጋሤ ፡ በጊዜ ፡ መዓት ፡ ወፈራሄ ፡ እምነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወራትዐ ፡ በሃይማኖቱ ፡ በውስተ ፡ ዓለም ። እስመ ፡ ዘቦቱ ፡ ሃይማኖት ፡ ወዐቂበ ፡ ርትዕ ፡ ወንጽሕ ፡ ይትከሀሎ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ማእከለ ፡ ዐበይት ፡ ወማእከለ ፡ አንስት ፡ ወላዕለ ፡ ንዋየ ፡ ድኩማን ፡ ወለእለ ፡ ሀለዉ ፡ ታሕተ ፡ ዘይሜግበሙ ፡ ወዘርኁቀ ፡ እምአድልዎ ፡ ገጽ ፡ ወለዘአጥረየ ፡ ህድአተ ፡ ወትዕግሥተ ፡ ወኢያስተሐቅርዎ ፡ ወኢያትሕቱ ፡ ፍትሐታቲሁ ፡ በእንተ ፡ ዘያገብእ ፡ ሎቱ ፡ እምነገር ፡ ዘየምዕዕ ። ወዳግማዊ ፡ ናሁ ፡ ተነግረ ፡ ውስተ ፡ አንቀጸ ፡ ሰማዕት ።

፩ሺ.፱፻፳ ኃምስ ፡ ይኩን ፡ ግዑዘ ፡ እስመ ፡ ዘኢኮነ ፡ ሥሉጠ ፡ ላዕለ ፡ መግዛተ ፡ ነፍሱ ፡ ኢይትክ



ስለሆነ ፡ ነው ። ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ እንደተናገረ ፡ (ኤፌ ፡ ፭ ፡ ፳፪) ። ከታችኛው ፡ ይልቅ ፡ ለላይኛው ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋል ። ወንድ ፡ አእምሮው ፡ የጸና ፡ ነውና ፡ ይፈርድም ፡ ዘንድ ፡ ለእርሱ ፡ ይገባዋል ። ሴት ፡ እንዳታስተምር ፡ ከካህናትም ፡ ቍጥር ፡ እንዳትሆን ፡ በመጻሕፍት ፡ እንደተነገረ ። ዳኛም ፡ ያለካህን ፡ አይሁን ።

፩ሺ.፱፻፲፯ ዳግመኛም ፡ ልብ ፡ ከእውቀቶቹ ፡ ጋር ፡ ነው ። (ያለው ፡ መሆን ፡ ነው) ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ እንስሳዊ ፡ ጠባይዕ ፡ ነው ። ሁለተኛውም ፡ ጠቃሚ ፡ ነው ። ሲሻውም ፡ የሚጠቀመው ፡ የለም ፡ በማገበር ፡ ወደርሱ ፡ በሚያንጋጥጥ ፡ ግንዛብ ፡ አይበቃም ። ይኸውም ፡ ትጋትን ፡ ለማግኘት ፡ የሚከታተል ፡ ሁኖ ፡ ሳለ ፡ ነው ። የፍርድን ፡ ልዩነት ፡ የሚያውቅና ፡ አእምሮ ፡ ያማረለት ፡ ከድንቁርና ፡ የራቀ ፡ በአእምሮውም ፡ መራቀቅ ፡ የጭንቅና ፡ የተሰወረውን ፡ የፍርድ ፡ ፍጻሜ ፡ ወደ ፡ መግለጽ ፡ የሚደርስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ። በአዋቆችና ፡ በከፉዎች ፡ መካከል ፡ የሚፈርድ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነውና ፡ ከእነርሱ ፡ ይልቅ ፡ ልቡን ፡ ያጣ ፡ ዕውቀት ፡ የጐደለው ፡ ሊሆን ፡ አይገባም ።

፩ሺ.፱፻፲፰ ሦስተኛ ፡ ኦርቶዶክሳዊ ፡ አማኝና ፡ በእርግጥም ፡ ካህን ፡ ይሁን ።

፩ሺ.፱፻፲፱ አራተኛ ፡ ለዳኞችና ፡ ለምስክሮች ፡ ቅን ፡ ሥራ ፡ መሥራት ፡ የሚገባ ፡ ነው ። መጀመሪያው ፡ ግን ፡ የታመነ ፡ ብልህ ፡ ከመነቀፍ ፡ የራቀ ፡ ከነውር ፡ የዳነ ፡ ለምሕረትና ፡ ለመውደድ ፡ ዝግ ፡ ያለ ፡ በቁጣ ፡ ጊዜ ፡ የሚታገሥ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ በዓለሙ ፡ ውስጥ ፡ በሃይማኖት ፡ የቀና ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ። ሃይማኖት ፡ ቅንነትና ፡ ንጽሕናንም ፡ መጠበቅ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ በአላዋቆችና ፡ በሴቶች ፡ መካከል ፡ በደኃ ፡ አደጎች ፡ ገንዘብም ፡ በሚያስተዳድራቸውም ፡ ሥር ፡ ሳሉት ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ይቻለዋልና ። ፊት ፡ አይቶ ፡ ከማድላት ፡ የራቀ ፡ ይሁን ። ፀጥታንና ፡ ትዕግሥትን ፡ ገንዘብ ፡ ያደረገውን ፡ ሰው ፡ አይናቁት ። ከሚያስቈጣው ፡ ነገር ፡ ወገን ፡ ስለሚመልሱለት ፡ ፍርዱን ፡ አያቃልሉ ። ሁለተኛውም ፡ እነሆ ፡ በአንቀጸ ፡ ሰማዕት ፡ ተነግሯል ።

፩ሺ.፱፻፳ አምስተኛ ፡ ነፃነት ፡ ያለው ፡ ይሁን ። ራሱን ፡ ለማስተዳደር ፡ ሥልጣን ፡ ያለው ፡ ያልሆነ ፡

አንቀጽ ፡ ማኅ ።

ሀሎ ፡ ከመ ፡ ይመጣብ ፡ ካልእኒሁ ።

፩ሺ፱፻፳፭ ሳድስ ፡ ይኩን ፡ ድኑን ፡ ምስማዕ ፡ ወንጹሐ ፡ ከመ ፡ ይፍልጥ ፡ ቃለ ፡ ጽድቅ ፡ ወቃለ ፡ ሐሰት ።

፩ሺ፱፻፳፮ ሳብዕ ፡ ይኩን ፡ ድኑን ፡ ልሳነ ፡ ወዘየአምር ፡ ነገረ ፡ ልሳን ፡ እንተ ፡ ኢትትከሀል ፡ ልሳነ ፡ ሰብእ ፡ ሚመጠ ፡ በዘይትናገሩ ፡ በበይናቲሆሙ ።

፩ሺ፱፻፳፯ ሳምን ፡ ተኀሥሦቱ ፡ ይቁም ፡ እንተ ፡ ትከልአ ፡ አብዝኆቶ ፡ ሰብእ ፡ ኀቤሁ ፡ በእንተ ፡ መፍቅድ ፡ ዘከመ ፡ ዝልጋስ ፡ እስመ ፡ ይትፈቀድ ፡ ከዊን ፡ ስማዕቱ ፡ ወተናብሮቱ ፡ በቅድመ ፡ ምኵናኑ ፡ ወአብዝኆ ፡ ሰብእ ፡ እለ ፡ ይትቄነዩ ፡ በን ቤሁ ።

፩ሺ፱፻፳፰ ታስዕ ፡ ይኩን ፡ ማእምረ ፡ ሕግ ፡ ወፍትሕ ፡ ዘተንእሥኡ ፡ በአሥራቲሃ ፡ ወበአዕጹቂሃ ። አሥራቲሃሰ ፡ ፬ቱ ፡ እሙንቱ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይኩን ፡ ዘየአምር ፡ ነገረ ፡ መጻሕፍት ፡ እምላከውያት ፡ ወአንቀጸቲሆን ፡ ወትርጓሜሆን ፡ ዘየኀብር ፡ ምስለ ፡ ጥያቄሆን ፡ አእምሮተ ፡ ዘያስተጋብእ ፡ ቦቱ ፡ ጠይቆተ ፡ ዘሀለወ ፡ ውስቴቱ እምፍትሐ ፡ ተንእሥአ ፡ ዘተከሥተ ፡ ወዘተሰወረ ፡ ሎሙ ፡ ወዘቀደመ ።

፩ሺ፱፻፳፱ ወካልእኒ ፡ ይሌቡ ፡ ነገረ ፡ መጻሕፍት ፡ ውኩፋት ፡ በአምሳለ ፡ ሐዋርያት ፡ ወእምማኅበራቲሆሙ ፡ ወካዕበ ፡ ቃለ ፡ ሢኖዶሳት ፡ ቅዱሳት ፡ ወዘአበው ፡ ቅዱሳን ፡ ከመ ፡ ይዕመድ ፡ እንከ ፡ ለነቢረ ፡ ቃላቲሆሙ ፡ ወተመስሎ ፡ ምግባራቲሆሙ ፡ ወለአእምሮስ ፡ ያበጽሕ ፡ ኀበ ፡ አእምሮተ ፡ ፍትሕ ።

፩ሺ፱፻፴ ወሣልስኒ ፡ ስእመ ፡ አእመረ ፡ ዘኮነ ፡ በእንቲአሁ ፡ ተጋብአተ ፡ ቀኖናት ፡ ወአበው ፡ ማእምራን ፡ ቅዱሳን ፡ ወዘተናፈቁ ፡ ውስቴቱ ፡ ከመ ፡ ይትሉ ፡ እሙንቱ ፡ ወያስተጋብእ ፡ ምክረ ፡ በእንተ ፡ ዘተፈልጠ ፡ ውስቴቱ ፡ ወየአኀዝ ፡ ዘኮነ ፡ እሙነ ፡ እመከፈልቲሁ ፡ ወዘይትረከብ ፡ ኀበ ፡ ተጋብኦ ፡ በእንቲአሁ ።

፩ሺ፱፻፴፩ ራብዕ ፡ አእምሮ ፡ ምግባረ ፡ ዘያበጽሕ ፡ ቦቱ ፡ ኀበ ፡ አእምሮ ፡ እኂበአተ ፡ አዕጹቅ ፡ እንተ ፡ ትትፈቀድ ፡ ኪያሃ ፡ ዘመስተራምም ፡ በእንቲአሃ ፡ ኀበ ፡ አሥራው ፡ እለ ፡ አሥራው ፡ ኪያሃ ። ወተጋብኦቶሙስ ፡ በእንተ ፡ ትርጓሜሃ ፡ ከመ ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

ሰጡ ፡ ሊሎቹን ፡ ሊያስተዳድር ፡ አይቻለውምና ፡

፩ሺ፱፻፳፭ ስድስተኛ ፡ ጆሮውና ፡ ዓይኑ ፡ ደኅና ፡ የሆነ ይሁን ። የዕውነትና ፡ የሐሰት ፡ ቃልን ፡ እንዲለይ ።

፩ሺ፱፻፳፮ ሰባተኛ ፡ እንደበቱ ፡ የረታና ፡ ቋንቋ ፡ የሚያውቅ ፡ ይሁን ። እርስበርሳቸው ፡ በሚነጋገሩ ፡ ገንዘብ ፡ የማትቻል ፡ የሸመቱ ፡ ሰዎች ፡ ቋንቋ ፡ ናት ።

፩ሺ፱፻፳፯ ስምንተኛ ፡ ስለሚያሻው ፡ ነገር ፡ ወደእርሱ ፡ የሰዎችን ፡ መሰብሰብ ፡ ከሚከለክል ፡ ደጁ ፡ መራቅ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ ደጁ ፡ ሥጋ ፡ ያለ ፡ ነው ። በሸንጎው ፡ ፊት ፡ የምስክሮችና ፡ የነገሮቹ ፡ መኖር ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የሚፋረዱትን ፡ ሰዎች ፡ ማብዛት ፡ ያስፈልጋልና ።

፩ሺ፱፻፳፰ ዘጠነኛ ፡ ሕግን ፡ የሥሩንና ፡ የቅርንጫፉንም ፡ የዳኝነት ፡ ፍርድ ፡ የሚያውቅ ፡ ይሁን ። ሥሮቹም ፡ አራት ፡ ናቸው ። ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ የቅዱሳት ፡ መጻሕፍትን ፡ ነገር ፡ ንባባቸውንና ፡ ክፍያቶቻቸው ፡ ጋር ፡ የሚተባበር ፡ ትርጓሜያቸውን ፡ ከቅጣቶች ፡ ፍርድ ፡ ወገን ፡ እስተደሙ ፡ የተገለጸውንና ፡ የተሰወረውን ፡ በውስጡ ፡ ያለውን ፡ መረዳት ፡ የሚሰበስብበት ፡ ዕውቀትንም ፡ የሚያውቅ ፡ ይሁን ።

፩ሺ፱፻፳፱ ሁለተኛም ፡ ከሐዋርያት ፡ ቃልና ፡ ከሥራቸውም ፡ የተነሣ ፡ ተቀባይነት ፡ ያላቸው ፡ የመጻሕፍትን ፡ ነገር ፡ ዳግመኛም ፡ የቅዱሳት ፡ ጉባኤያትንና ፡ የቅዱሳን ፡ አባቶችን ፡ ቃል ፡ ያስተውል ። ትእዛዛቸውን ፡ ለመሥራትና ፡ በሥራቸውም ፡ ለመምሰል ፡ ዕሙድ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ። ማወቅስ ፡ ፍርድን ፡ ወደማወቅ ፡ ያደርሳል ።

፩ሺ፱፻፴ ሦስተኛውም ፡ የመጻሕፍት ፡ መሰብሰብና ፡ ዐዋቆች ፡ የሆኑ ፡ ቅዱሳን ፡ አባቶች ፡ ስለእርሱ ፡ የተባበሩበትን ፡ በውስጡም ፡ የተለያዩበትን ፡ ቢያውቅ ፡ ነው ፡ እውነተኛውን ፡ ይከተል ፡ ዘንድ ። በውስጡም ፡ ስለተለያዩበት ፡ አስተያየቱን ፡ ይመረምር ፡ ዘንድ ። ከተለያዩበት ፡ እውነተኛ ፡ የሆነውንና ፡ እንደ ፡ ወደሆኑበት ፡ የሚቀርበውን ፡ ይያዝ ።

፩ሺ፱፻፴፩ አራተኛው ፡ ስለእርሱ ፡ በጥ ፡ የምታደርግ ፡ የምትወደድ ፡ እዕውቅን ፡ እርሷን ፡ ወደእስተኛ ወደአሥራው ፡ መመለስን ፡ ወደማወቅ ፡ የሚያደርስ ፡ ልክን ፡ ማወቅ ፡ ነው ። ስለትርጓሜዋ ፡ መሰብሰባቸው ፡ ግን ፡ በየሁኔታቸው ፡ የሚ

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ይጺሖ ፡ ፍኖተ ፡ አእምሮ ፡ ዘፍትሐ ፡ ኩነኔ ሆሙ ፡ ለመጻእያን ፡ በበኩነቶሙ ። እስመ ፡ ዘለበወ ፡ አእምሮቶሙ ፡ ለእሉ ፡ ፬ቱ ፡ አሥራው ፡ ይከውን ፡ እምስብአ ፡ እለ ፡ የአምሩ ፡ ፍትሐ ፡ ወእለ ፡ ያስተሐምሙ ፡ ቦቱ ፡ በፍጻሜ ፡ አበይና ፡ ወእለብዎ ፡ ወብዉሕ ፡ ሎቱ ፡ ይረሲ ከመ ፡ ይተርጕም ፡ ወይፍታሕ ፡ ፍትሐ ።

፩ሺ.፬፻፹፰ ዓሥር ፡ ለያእምር ፡ ዘይሠይሞ ፡ ፈታሒ ፡ ዘሀቀበ ፡ እሎንተ ፡ ትእዛዛተ ፡ እመሂ ፡ በዘአቅደመ ፡ አእምሮተ ፡ ግዕዙ ፡ እው ፡ በኅርየ ፡ እው በሐተታ ፡ ወኀሢሥ ፡ እምእለ ፡ የአምር ፡ ኪያሆሙ ።

፩ሺ.፬፻፹፱ ፲ወ፩ዱ ፡ ዘጸሐፉ ፡ ሎቱ ፡ መጽሐፈ ፡ መባሕት ፡ ለአወፍዮቱ ፡ ኩነኔ ፡ ፍትሕ ፡ ወተፀምዶቱ ፡ ውስቴታ ፡ ወእምዝ ፡ ያግህዱ ፡ ዘንተ ፡ ወያሰምዑ ፡ ሎቱ ።

፩ሺ.፬፻፺ ፲ወ፪ቱ ፡ ቃለ ፡ ምህሮሁ ፡ ሶበ ፡ አወፈይዎ ፡ መጽሐፈ ፡ መባሕት ፡ እመሂ ፡ በንባቡ ፡ እው ፡ በሕገጊሁ ፡ ውስተ ፡ ርእይ ።

፩ሺ.፬፻፺፩ ፲ወ፫ቱ ፡ ኢይክልእዎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ለእለ ፡ ውስተ ፡ ሢመቱ ፡ እው ፡ ለመብዝኅቶሙ ፡ ለመጺአ ፡ ኀቤሁ ፡ ወኢይእበይ ፡ ኵሉ ፡ ዘውስተ ፡ ሢመቱ ፡ እው ፡ መብዝኅቶሙ ፡ በእንተ ፡ ከመ ፡ ይሠየም ፡ ላዕሌሆሙ ።

፩ሺ.፬፻፺፪ ምስራፍ ፡ ዳግማዊ ፡ በእንተ ፡ ሥርዓቱ ፡ ለእመስኬ ፡ ኮነት ፡ ሢመቱ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ይከውን ፡ ሥሉጠ ፡ ላዕለ ፡ ሰብዑ ፡ ኩነኔያት ። እሉቱ ፡ እምኔሆን ፡ ፈሊጠ ፡ ጋእዝ ፡ ወመተረ ፡ ባእስ ፡ እመሂ ፡ በተሳልሞ ፡ ወዕርቅ ፡ እንዘ ፡ ይማመሩ ፡ እው ፡ በግብር ፡ ፈሪሆሙ ።

፩ሺ.፬፻፺፫ መካልኢትኒ ፡ ካዕበ ፡ አብጽሖተ ፡ ንዋያት ፡ ኀበ ፡ እለ ፡ ይደልዎሙ ፡ ሶበ ፡ ጸንዐት ፡ በእምነተ ፡ አፉሁ ፡ እው ፡ በአጠይቆ ፡ ሰማዕት ።

፩ሺ.፬፻፺፬ ወሣልሲት ፡ ከዊነ ፡ አመግቦ ፡ ላዕለ ፡ ዘይክልእዎ ፡ አስተዋፅኦተ ፡ ንዋይ ፡ እመኒ ፡ በእንተ ፡ ናእስ ፡ እው ፡ በእንተ ፡ ሰበዱ ፡ እው ፡ በእንተ ፡ ተሣልቆቱ ፡ ከመ ፡ ይትዐቀብ ፡ ንዋዮሙ ፡ በዘ ይደሉ ፡ ወበእንተ ፡ ጠይቆተ ፡ ፍትሕ ።

፩ሺ.፬፻፺፭ ወራብዒት ፡ በእንተ ፡ አእምሮ ፡ ገዜያት ፡ ዘቈጺረ ፡ ጕልታት ፡ ለሀቂበ ፡ ሥረዊሃ ፡ ወፈሊጠ ፡ አዕጹቂሃ ፡ ወኀሢአ ፡ ዘይትረከብ ፡ እም

ስለ ፡ ዳኛ ።

መጡ ፡ የቅጣቶችን ፡ ፍርድ ፡ የማወቅን ፡ ጕዳና ጥርጊያ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። እሊህን ፡ አራቱን ፡ አሥራው ፡ ማወቅን ፡ ያስተዋለ ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ ከሚያውቁ ፡ ፍርድንና ፡ ማስተዋል ንም ፡ በመፈጸም ፡ ከሚተጉ ፡ ሰዎች ፡ ወገን ፡ ይሆናልና ። እንዲተረጕም ፡ ፍርድም ፡ እንዲፈ ርድ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፬፻፹፰ አሥረኛ ። የሚሾመው ፡ ዳኛ ፡ አስቀድሞ ፡ ጠባዩን ፡ በማወቅ ፡ ወይም ፡ በምርጫ ፡ ወይም ፡ እነርሱን ፡ ከሚያውቋቸው ፡ ሰዎች ፡ በመጠየቅና ፡ በመመርመር ፡ እሊህን ፡ ትእዛዛት ፡ የጠበቀ ፡ መሆኑን ፡ ይወቅ ።

፩ሺ.፬፻፹፱ ፲፩ኛ ። የፍርድ ፡ ቅጣት ፡ ለመስጠትና ፡ በውስጡም ፡ በሹመቱ ፡ ጸንቶ ፡ ለመኖር ፡ ለማገልገሉ ፡ የመብት ፡ ደብዳቤ ፡ ለጻፉለት ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ይህን ፡ ይግለጹለት ። ዓዋጅም ፡ ያናግሩለት ።

፩ሺ.፬፻፺ ፲፪ኛ ። የመብት ፡ ደብዳቤ ፡ በሰጡት ፡ ጊዜ ፡ ንባቡን ፡ ወይም ፡ ሕጉን ፡ በመመልከትም ፡ ቢሆን ፡ የማስተማሩ ፡ ነገር ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፺፩ ፲፫ኛ ። በሹመቱ ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወይም ፡ ብዙዎችን ፡ ወደእርሱ ፡ ለመምጣት ፡ አይከልክልዋቸው ። በሹመቱ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወይም ፡ አብዛኞዎቹ ፡ በላያቸው ፡ ስለሚሾምባቸው ፡ እንቢ ፡ አይበሉ ።

፩ሺ.፬፻፺፪ ሁለተኛ ፡ ምዕራፍ ። ስለ ፡ ሥርዓቱ ፡ ይናገራል ። ሹመቱ ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ከሆነች ፡ በሰባቱ ፡ ቅጣቶች ፡ ላይ ፡ የሠለጠነ ፡ ይሆናል ። ከእነርሱም ፡ አንዲቱ ፡ በፍቅርና ፡ በዕርቅም ፡ ቢሆን ፡ ተስማምተው ፡ ወይም ፡ በግድ ፡ ፈርተውም ፡ ቢሆን ፡ ፀብ ፡ ክርክርን ፡ ማራቅ ፡ ነው

፩ሺ.፬፻፺፫ ሁለተኛዪቱ ፡ ደግሞ ፡ በአፉ ፡ በማመን ፡ ወይም ፡ በምስክር ፡ በማስረዳት ፡ በጸናች ፡ ጊዜ ፡ ገንዘብን ፡ ለሚገባቸው ፡ ማድረስ ፡ (ማካፈል) ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፺፬ ሦስተኛዪቱ ። ስለሕፃንነቱ ፡ ወይም ፡ ስለአላዋቂነቱ ፡ ወይም ፡ ስለዋዘኛነቱ ፡ ገንዘቡን ፡ ከማወጣጣት ፡ በሚከለክሉት ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ የማስተዳደር ፡ ሁኔታ ፡ ነው ። ገንዘባቸው ፡ በሚገባ ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ ፍርዱንም ፡ ስለ ፡ መረዳት ።

፩ሺ.፬፻፺፭ አራተኛዪቱ ። ጕልቶች ፡ የሚቈጠሩበትን ፡ ጊዜያት ፡ ስለማወቅ ፡ ሥሯን ፡ ለመጠበቅና ፡ ቅርንጫፏን ፡ ስለመለየት ፡ ከእርሷ ፡ የሚገኘው

ኔሃ ፡ ወእስተዋጽኦቶ ፡ በእንተ ፡ ፍናዋቲሃ ። ወእመኒ ፡ ኮነ ፡ ድልወ ፡ ለአመማቦታ ፡ ይትኖለው ፡ አው ፡ ይሢሞ ፡ ወእምዝ ፡ ያእምር ፡ እማኅፀንት ፡ ዘሀለወ ፡ ታሕተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለመግብት ፡ ወእምዝ ፡ ግብረ ፡ ይኩትም ፡ ወእለ ፡ ሀለዉ ፡ ታሕተ ፡ ምግብና ።

፩ሺ.፬፻፴፮ ኃምሲት ፡ ግቢረ ፡ ትእዛዛት ፡ በከመ ፡ ወሰነ ፡ አዛዚ ፡ ወባቲ ፡ አብሖት ፡ ሕግ ፡ እንበለ ፡ ተከልአ ፡ ወአመሰ ፡ ቦ ፡ ዘአዘዘ ፡ ሎቱ ፡ ኪያሃ ፡ ይኩን ፡ ኖላዌ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ ይሢም ።

፩ሺ.፬፻፴፯ ሳድሲት ፡ እትልዎ ፡ ለዘይሜኒ ፡ ለፍትሕ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ በምግባር ፡ ዐቢየ ፡ ወኢይከውኖ ፡ ለዘእትለዎ ፡ ለእመ ፡ አትለወ ፡ ካልአ ፡ ዘኢነገረ ፡ ውእቱ ፡ ሎቱ ። ወእምድኅረ ፡ ሞቱ ፡ ሥዩም ፡ ዘይበቍዕ ፡ ለሢመተ ፡ ፍትሕ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ግብረ ፡ ዐቢየ ፡ ወአልቦቱ ፡ ሥልጣን ፡ ከመ ፡ ይሢም ፡ ይሠየም ፡ እምነበ ፡ ካልኡ ፡ ዘቦቱ ፡ መባሕት ፡ ለዝንቱ ።

፩ሺ.፬፻፴፰ ሳብዒት ፡ ጥያቄ ፡ ስማዕት ፡ ለይኩኑ ፡ ንጹሓነ ፡ እለ ፡ ይከውኑ ፡ ስምዐ ፡ ወእለ ፡ የአምንዎሙ ፡ ወእለ ፡ ኮኑ ፡ ኄራነ ፡ እምላእካኒሁ ፡ ወኅሩይ ፡ ዘእምታሕቴሁ ፡ ከመ ፡ ያንብሮ ፡ ምስለ ፡ ጽንዐት ፡ ወሃይማኖት ፡ ወከመ ፡ ይወልጥ ፡ ሀየንቴሆሙ ፡ እመ ፡ አስተርአዮ ፡ ሀኬት ፡ ወስኢን ፡ ላዕሌሆሙ ።

፩ሺ.፬፻፴፱ ወለአመሰ ፡ ኮነት ፡ ሢመቱ ፡ እምርት ፡ ዲበ ፡ ጽዱ ፡ ግብር ፡ ዘእንበለ ፡ ካልኢ ፡ ይከውን ፡ ሕጹጸ ፡ ሢመቱ ፡ ዘኢሁ ፡ ከመ ፡ ዘተውህደሙ ፡ ለአውስበ ፡ ብእሲት ፡ ወአኮ ፡ ላዕለ ፡ ንዋይ ፡ አው ፡ ላዕለ ፡ አሐቲ ፡ ሀገር ፡ ዘእንበለ ፡ አድያሚሃ ፡ ወላዕለ ፡ ሕዝብ ፡ ኅቡር ፡ እምስብእ ፡ ዘእንበለ ፡ ካልአኒሆሙ ፡ በእንተ ፡ ዘአእመረ ፡ ልሳኖ ፡ ብሔሮሙ ፡ ወፍጥረቶሙ ፡ ዘእንበለ ፡ ካልአኒሁ ፡ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይትበደሙ ፡ ዘንቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ዳእሙ ፡ በምግብና ።

፩ሺ.፬፻፵ ምዕራፍ ፡ ፫ቱ ፡ በእንተ ፡ ዘይኤዝዝዎ ፡ ቦቱ ፡ ይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ “ኢትፍትሑ ፡ በአድልዎ ፡ አላ ፡ ፍትሕ ፡ ጽድቀ ፡ ፍትሑ ።”

፩ሺ.፬፻፵፩ ድስቅ ፡ ዘ፩ቱ ፡ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡



ንም ፡ ስለመውሰድ ፡ ስለሥራዎቿም ፡ ስለማወጣጣት ፡ ይናገራል ። እርሷን ፡ ለማስተዳደር ፡ የሚገባ ፡ ቢሆን ፡ ይጠብቃት ። ወይም ፡ ይሹም ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከአደራ ፡ ወገን ፡ በሹማምቱ ፡ እጅ ፡ ያለውን ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የድኃ ፡ አደጉንና ፡ በትድድር ፡ ሥር ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ሥራ ፡ ይወቅ ።

፩ሺ.፬፻፴፮ አምስተኛዪቱ ፡ አዛዥ ፡ እንደወሰነ ፡ ትእዛዙን ፡ ማድረግ ፡ ነው ። በእርሷም ፡ ያለመከልከል ፡ ሕግ ፡ አዝዛለች ። እርሷን ፡ ያዘዘለት ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ግን ፡ ጠባቂ ፡ ይሁን ። ይህም ፡ ባይሆን ፡ ይሹም ።

፩ሺ.፬፻፴፯ ስድስተኛዪቱ ፡ በሥራ ፡ ታላቅ ፡ ቢሆን ፡ ለፍርድ ፡ የሚስማማውን ፡ ምክትል ፡ ማድረግ ፡ ነው ። ምክትል ፡ ላደረጉት ፡ እርሱን ፡ ያልነገረለትን ፡ (ያልፈቀደለትን) ፡ ሌላውን ፡ ምክትል ፡ ቢያደርግ ፡ አይገባውም ። ለፍርድ ፡ ሹመት ፡ የሚጠቅም ፡ ዳኛ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ሥራው ፡ ታላቅም ፡ ቢሆን ፡ ሊሾም ፡ ሥልጣን ፡ የለውም። ለዚህ ፡ መብት ፡ ካለው ፡ ከሌላው ፡ ይሾም ፡ እንጂ ።

፩ሺ.፬፻፴፰ ሰባተኛዪቱ ፡ የምስክሮች ፡ ማስረጃ ፡ ናት ። ምስክር ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ንጹሐንና ፡ የሚያምኗቸው ፡ ይሁኑ ። ከአገልጋዮቹ ፡ ደጋግ ፡ የሆኑት ፡ ከበታቹ ፡ ያለው ፡ ምርጥ ፡ በሃይማኖት ከመጽናት ፡ ጋር ፡ ያኖረው ፡ ዘንድ ፡ ስንፍና ፡ ድካም ፡ በተገለጠባቸው ፡ ጊዜ ፡ ስለእነርሱ ፡ ይለውጥ ፡ ዘንድ ።

፩ሺ.፬፻፴፱ ሹመቱ ፡ በሌላው ፡ ሳይሆን ፡ በአንድ ፡ ሥራ ፡ የታወቀች ፡ ብትሆን ፡ ሹመቱ ፡ ጐደሎ ፡ ይሆናል ። በገንዘብ ፡ ያይደለ ፡ ሚስት ፡ ለማግባት ፡ ወይም ፡ በዙሪያዋ ፡ ሳይሆን ፡ በአንዲት ፡ መንደር ፡ ከባልንጀሮቹ ፡ ተለይቶ ፡ ቋንቋቸውንና ፡ ትውልዳቸውን ፡ ስላወቀ ፡ በመላው ፡ ሳይሆን ፡ ከሰዎች ፡ በ፩ ፡ ወገን ፡ እንደተሾመ ፡ ሰው ፡ በሹመት ፡ ቢሆን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ይህን ፡ ሊተላለፍ ፡ አይገባውም ።

፩ሺ.፬፻፵ ሦስተኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ስለሚያዝዙበት ፡ ይናገራል ። ጌታችን ፡ በቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ እውነተኛ ፡ ፍርድ ፡ ፍረዱ ፡ እንጂ ፡ በአድልዎ ፡ አትፍረዱ ፡ አለ ። (ዮሐ ፡ ፯ ፡ ፳፬) ።

፩ሺ.፬፻፵፩ ድስቅ ፡ ፩ ። ቅንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡

ራትዐ ፡ ወተላዌ ፡ ፈቃዱ ፡ ለእግዚአብሔር ። ዘ፯፡ ወነዋ ፡ ተጽሕፈ ፡ ውስተ ፡ መዝሙር ፡ "ወርትዐ ፡ ፍትሑ ፡ እ ፡ ደቂቀ ፡ እጓለ ፡ እመ ሕያው" ። ዘ፲፡ ወካዕበ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ ኢታድሉ ፡ ለገጸ ፡ ባዕል ፡ በውስተ ፡ ፍትሕ ፡ ወኢትምሐሮ ፡ ለነዳይ ፡ እስመ ፡ ለፍ ትሕ ፡ አልቦ ፡ ውስቴቱ ፡ ምሕረት ፡ ወእእምሩ ዅሉ ፡ ዅሉን ፡ ኃጣውእ ፡ ዘዘዚአሃ ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ እምኔክሙ ፡ ዐመፃ ፡ ለፈዱ ፡ ከመ ፡ ኢይትነሣእ ፡ ላዕሌክሙ ፡ መዓተ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ በእንተ ፡ ፍትሐ ፡ ዐመፃ ፡ ዘእንትሙ ፡ ፈታሕክሙ ፡ ወውእቱ ፡ ይሴአለክሙ ።

፩ሺ.፬፻፵፪ ወተዐቀቡ ፡ እምተመስሎ ፡ በረበናት ፡ ዘካህ ናት ፡ እለ ፡ ኮኑ ፡ ስምዐ ፡ ላዕለ ፡ ሶስና ፡ በባቢ ሎን ፡ ወፈትሑ ፡ ላዕሌሃ ፡ ፍትሐ ፡ ሞት ፡ በዐ መፃ ፡ ከመ ፡ ኢትኩኑ ፡ ድልዋነ ፡ ለዅኔ ፡ እም ፈታሒት ። እስመ ፡ ለሶስና ፡ አድኅና ፡ እግዚ አብሔር ፡ እምእደዊሆሙ ፡ ለዐላውያን ፡ ሕግ ፡ በእደ ፡ ዳንኤል ፡ ነቢይ ፡ ወለእልክቱሰ ፡ ረበ ናተ ፡ ካህናት ፡ ቀተሎሙ ፡ በእንተ ፡ ዘአበሱ ፡ ላዕሌሃ ፡ ወወድዮሙ ፡ ውስተ ፡ ዅኔ ፡ እሳት ።

፩ሺ.፬፻፵፫ ወእግዚአብሔርሰ ፡ የአምር ፡ ፍትሐክሙ ፡ ዘትፈትሑ ፡ ቦቱ ፡ ወኢይትከሀለክሙ ፡ ትጉ ብኡ ፡ እምኔሁ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ርቱዐ ፡ ፍትሕ ክሙ ፡ ትረክቡ ፡ ለጌሠ ፡ ሠናየ ፡ በርትዕ ፡ እም ኔሁ ፡ በዝ ፡ ዓለም ፡ ወበዘይመጽእኒ ። ወለእ መሰ ፡ ኮነ ፡ ፍትሕክሙ ፡ በዐመፃ ፡ ትረክቡ ፡ እከየተ ፡ ብዙኃተ ።

፩ሺ.፬፻፵፬ ወእአምሩ ፡ ከመ ፡ ፍርሃተ ፡ ገጽ ፡ ይመጽእ ፡ በነሢእ ፡ እምኃ ፡ ወሕልያን ፡ ወትከውኑ ፡ ከማ ሆሙ ። ይደሉ ፡ ከመ ፡ ኢትትወከፍ ፡ እምኃ ፡ እምእሐዱኒ ፡ ሰብ ፡ ትሁብ ፡ ሚመተ ፡ ዘእንበለ ፡ አምኀበ ፡ ዘእልቦቱ ፡ መባሕት ፡ ዘከመ ፡ ወልድ ወወላዲ ።

፩ሺ.፬፻፵፭ ወይደልዎ ፡ ከመ ፡ የአዝዞ ፡ ለዘይትልዎ ፡ በዘ ተአዘዘ ፡ ቦቱ ፡ ውእቱ ፡ ወከመ ፡ የአዝዞሙ ፡ ለላእካኒሁ ፡ ወለመገብቱ ፡ በዮንቱሁ ፡ በፈሪሀ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወበአስተሐምሞ ፡ በእንተ ፡ ኀሢሥ ፡ ንዋያት ። ወየአዝዞሙ ፡ ለመርዳእያ ኒሁ ፡ ለምሒክ ፡ በተጻልኦ ፡ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይትገበር ፡ ውስተ ፡ መካነ ፡ ምኵናን ፡ ተግ



የሚከተል ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ። ፯ ። በመዝሙ ርም ፡ እነሆ ፡ ተጽፏል ። የሰው ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፡ እውነት ፡ ፍረዱ ። (መዝ ፡ ፶፰ ፡ ፩) ። ፲ ፡ ዳግ መኛም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ። በፍ ርድ ፡ ጊዜ ፡ ለባለጸጋ ፡ ፊት ፡ አታድላ ። ለድኃ ውም ፡ አትዘንለት ፡ አለ ፡ በፍርድ ፡ ውስጥ ፡ ምሕረት ፡ የለምና ። (ዘሌ ፡ ፲፱ ፡ ፲፭) ። ከእናንተ በአንዱ ፡ ላይ ፡ በደል ፡ እንዳይሆን ፡ የኀጢአቶ ችን ፡ ሁሉ ፡ ፍርድ ፡ በየራሷ ፡ እወቁ ። እናንተ ፡ በፈረዳችሁት ፡ የዓመፅ ፡ ፍርድ ፡ የእግዚአብሔ ር ፡ መዓት ፡ በላያችሁ ፡ እንዳይመጣ ፡ እርሱም ፡ ይጠይቃችኋል ።

፩ሺ.፬፻፵፪ በባቢሎን ፡ በሶስና ፡ ላይ ፡ የሐሰት ፡ ምስክ ሮች ፡ የሆኑና ፡ በዓመፅ ፡ የሞት ፡ ፍርድ ፡ የፈረ ዱባትን ፡ የካህናት ፡ መምህራንን ፡ ከመምሰል ፡ ተጠበቁ ። ከዳኞች ፡ ለቅጣት ፡ ዝግጁዎች ፡ እን ዳትሆኑ ። እግዚአብሔር ፡ ሶስናን ፡ በነቢይ ፡ ዳንኤል ፡ ቃል ፡ ከሕግ ፡ አፍራሾች ፡ እጅ ፡ አድ ኗታልና ። እነዚህን ፡ የካህናት ፡ መምህራንን ፡ ግን ፡ በእርሷ ፡ ላይ ፡ ስለበደሉ ፡ ገደላቸው ። ወደእሳት ፡ ቅጣትም ፡ ጨመራቸው ። (ተረ ፡ ዳን ፡ ፶፰ - ፷፩) ።

፩ሺ.፬፻፵፫ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ የምትፈርዱትን ፡ ፍርድ ፡ ያውቅባችኋል ። ከእርሱም ፡ ልትሸሽጉ ፡ አትችሉም ። ፍርዳችሁ ፡ የቀና ፡ ቢሆን ፡ በእው ነት ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ በሚመ ጣውም ፡ ዓለም ፡ መልካም ፡ ዋጋ ፡ ታገኛላችሁ። ፍርዳችሁ ፡ በዓመፅ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ፍዳ ፡ ታገኛላችሁ ።

፩ሺ.፬፻፵፬ ፊት ፡ አይቶ ፡ ማድላት ፡ እጅ ፡ መንሻንና ፡ መማለጃን ፡ በመቀበል ፡ እንደሚመጣ ፡ እወቁ ። እንደ ፡ እነርሱም ፡ ትሆናላችሁ ። ሹመት ፡ በሰ ጠሽው ፡ ጊዜ ፡ ካንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ እንዳትቀበል ፡ ይገባል ። መብት ፡ ከሌ ለው ፡ ዘንድ ፡ ቢሆን ፡ ነው ፡ እንጂ ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ ልጆችና ፡ እንደ ፡ አባት ፡ ያለ ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፵፭ ምክትሉን ፡ እርሱ ፡ በታዘዘበት ፡ ሊያዝዘው ፡ አገልጋዮችንና ፡ ሹማምቱንም ፡ እግዚአብሔ ርን ፡ በመፍራትና ፡ ገንዘብን ፡ ስለመሻት ፡ በመ ትጋት ፡ ስለእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ሊያዝዛቸው ፡ ይገ ባል ። ረዳቶቹንም ፡ በጠብ ፡ ጊዜ ፡ ስመራራት ይዘዛቸው ። በሸንጎው ፡ ቦታ ፡ መገበያየት ፡ ወይም ፡ መሻረክ ፡ ወይም ፡ ይህን ፡ የሚመስለው

አንቀጽ ፡ ፶፫ ።

ያ.ቡ ፡ ወኢ ፡ ተሳትፎ ፡ ወኢ ፡ ዘይመስሎ ፡ ለገዛ ንቱ ፡ ኢ ፡ ለነፍሱ ፡ ወኢ ፡ ለመጋቢሁ ፡ ዘለዉቅ ፡ ሎቱ ፡ ወከመ ፡ ኢይትወከፍ ፡ ፩ዱ ፡ እም ተጻላእያን ፡ ዘእንበለ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ወኢ ፡ እምድኅረ ፡ ተፈልጦቶሙ ።

፩ሺ.፩፻፵፮ ምዕራፍ ፡ ራብዕ ፡ በእንተ ፡ ትእዛዛተ ፡ ፍትሖ ። ይደልዎ ፡ ቅድመ ፡ ከመ ፡ ያስተርኢ ፡ መጽሐፈ ፡ ሢመቱ ፡ ወይትነበብ ፡ በውስተ ፡ መካነ ፡ ምኵናን ፡ ከመ ፡ ያስማዕ ፡ ዜናሁ ፡ ወእምዝ ፡ ያዕርጉ ፡ ሎቱ ፡ ነገረ ፡ ምክንያቶሙ ፡ ለሙቁሓን ፡ ወለዕለ ፡ ሀለዉ ፡ በግዘት ፡ ይፍታሕ ፡ ለዘይደልዎ ፡ ፍትሐት ፡ እምኔሆሙ ፡ ወይኅድግ ፡ ለዘኢይደልዎ ፡ ፍትሐት ። ወእመኒ ፡ በእንተ ፡ ተአምኖቱ ፡ ወበስምዕ ፡ ዘኮነ ፡ ሎቱ ፡ አው በእንተ ፡ አበይዎ ፡ ላዕሌሁ ።

፩ሺ.፩፻፵፯ ወለዘኒ ፡ ይቤ ፡ ግፉዕ ፡ አነ ፡ ወኢሀለወ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ከመ ፡ የሐድስ ፡ ተኳንኖቶ ፡ ይጽሐፍ ፡ መልእክተ ፡ ኀበ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ከመ ፡ ይብጻሕ ፡ ለተኳንኖ ፡ ለእመ ፡ ሀለወ ፡ በመካን ፡ ቅሩብ ፡ ወለእመ ፡ ተድኅረ ፡ ይፍትሖ ፡ ወይፈንዎ ፡ እምድኅረ ፡ ወሀበ ፡ ትሕቢተ ። ወለዘሂ ፡ ተጠየቀ ፡ ከመ ፡ ነዳይ ፡ ውእቱ ፡ ይንሣእ ፡ እምኔሁ ፡ ተሐባዪ ፡ ከመ ፡ ይፍትሖ ፡ እስከ ፡ አመ ፡ ይረክብ ፡ ዘይፈዲ ፡ ሎቱ ፡ ዘተለቅሐ ። ወእምዝ ፡ የአዝዞሙ ፡ ለላእካኒሁ ፡ ከመ ፡ ኢያብኡ ፡ ኀቤሁ ፡ ዕድወ ፡ ዘእንበለ ፡ እድዉ ፡ ወኢ ያቅድሙ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ እምበዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ወኢ ፡ ለዘተድኅረ ፡ እምነ ፡ ዘቀደመ ።

፩ሺ.፩፻፵፰ ወይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ሀዱእ ፡ ወኢ ተዓባዬ ፡ ወኢይፍታሕ ፡ እንዘ ፡ ቦቱ ፡ ዘያማስኖ ፡ ለሕሊናሁ ፡ ዘከመ ፡ ቍጥዓ ፡ ወፍርሃት ፡ መዘውካን ። ወዘከመ ፡ ኀዘን ፡ ወፍሥሓ ፡ መርሰዓን ፡ ወዘከመ ፡ ረኃብ ፡ ወጽምእ ፡ ነካይያን ፡ ወዘከመ ፡ ደዌ ፡ ወሕማም ፡ አሕማምያን ። ወዘከመ ፡ ንዋም ፡ ወድቃስ ፡ መዋዕያን ፡ ወዘከመ ፡ ሀኬት ፡ ወድካም ፡ አሕማምያን ፡ ወበስካርኒ ፡ ወቅሳሴ ፡ ውተእንትሎ ፡ እምብዝኀ ፡ ፈቲሐ ፡ ፍትሕ ። ወኢይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይሠውር ፡ ዘእንበለ ፡ ጊዜያት ፡ ለሰረፍት ፡ ወለገቢረ ፡ መፍቅዳት ።

፩ሺ.፩፻፵፱ ወእምከመ ፡ በጽሖ ፡ ኀቤሁ ፡ ተጻላእያን ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

ለራሱ ፡ ወይም ፡ ለታወቀው ፡ ሹመ ፡ ሊደረግ ፡ አይገባም ። ከጠበኞች ፡ ሰዎች ፡ አንዱን ፡ ያለባላጋራው ፡ ወይም ፡ ከተለያዩ ፡ በኋላ ፡ ሊቀበል ፡ አይገባም ።

፩ሺ.፩፻፵፮ ፩ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ስለፍርዱ ፡ ትእዛዛት ፡ ይናገራል ። አስቀድሞ ፡ ወሬው ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፡ የሹመቱ ፡ ደብዳቤ ፡ በአደባባይ ፡ ሊታይና ፡ ሊነበብ ፡ ይገባል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የታሠሩትን ፡ ሰዎችና ፡ በግዞት ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ምክንያት ፡ ነገር ፡ ይንገሩት ። በእርሱ ፡ ሥልጣን ፡ ሊፈታ የሚገባውን ፡ ይፍታ ። መፈታት ፡ የማይገባውን ያቆየው ። ስለመታመኑና ፡ ስለ ፡ ተመሰከረለት ፡ ወይም ፡ ስለተፈረደበት ፡ ቢሆን ።

፩ሺ.፩፻፵፯ ከርክሩን ፡ ያድስ ፡ ዘንድ ፡ ባላጋራው ፡ በሌለበት ፡ እኔ ፡ ተበድያለሁ ፡ ቢል ፡ ወደ ፡ ባላጋራው ፡ ደብዳቤ ፡ ይጻፍ ። በቅርብ ፡ ቦታ ፡ ካለ ፡ ለመፈራረድ ፡ ይድረስ ፡ ዘንድ ። ቢቀር ፡ ዋስ ፡ ከሰጠ ፡ በኋላ ፡ ፈትቶ ፡ ይስደደው ። ደኃ ፡ እንደሆነ ፡ ለታወቀ ፡ ሰው ፡ የተበደረውን ፡ የሚከፍልበት ፡ እስኪያገኝ ፡ ድረስ ፡ ከእርሱ ፡ ዋስ ፡ ይቀበል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አጋፋሪዎቹን ፡ ባላጋራውን ፡ ከባላጋራው ፡ ለይተው ፡ ወደእርሱ ፡ እንዳያስገቡ ፡ ባለዕዳን ፡ ከባለዕዳው ፡ የኋለኛውንም ፡ ከቀደመው ፡ እንዳያስቀድሙ ፡ ይዘዛቸው ።

፩ሺ.፩፻፵፰ ፀጥ ፡ ያለ ፡ የማይታበይ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። አሳቡን ፡ የሚለውጥ ፡ ነገር ፡ እያለበት ፡ አይፍረድ ። ይኸውም ፡ እንደሚያውኩ ፡ እንደ ፡ ቁጣና ፡ እንደ ፡ ፍርሃት ፡ እንደሚያዘንጉ ፡ እንደ ፡ ኀዘንና ፡ እንደ ፡ ደስታ ፡ እንደሚነኩ ፡ እንደ ፡ ረኀብና ፡ እንደ ፡ ፅምእ ፡ እንደሚያሳምሙ ፡ እንደ ፡ ደዌና ፡ እንደ ፡ ሕማም ፡ ድል ፡ እንደሚነሡ ፡ እንደ ፡ እንቅልፍና ፡ እንደ ፡ ሽልብታ ፡ እንደሚያሳዝኑ ፡ እንደስንፍናና ፡ እንደ ፡ ድካም ፡ ያሉ ፡ ናቸው ። በስካርና ፡ በመቅለል ፡ ፍርድን ፡ ከመፍረድ ፡ ብዛት ፡ የተነሣም ፡ በመሰልቸት ፡ አይፍረድ ። ለዕረፍትና ፡ ፈቃድን ፡ ለመፈጸም ፡ በተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ ካልሆነም ፡ በቀር ፡ ሊሰወር ፡ አይገባውም ።

፩ሺ.፩፻፵፱ የተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ ወደእርሱ ፡ ከመጡ ፡ ሺማሪ

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ንቲአሆን ፡ አበው ፡ በአእምሮ ፡ ዘአጥረይዎ ፡ እሙ ፡ ዘይመስሎ ፡ ለልቡናሁ ፡ አእምር ፡ እስመ ፡ ተመይጦተ ፡ ርትዕ ፡ ይኄይስ ፡ እምተኃልፎ ፡ ላዕለ ፡ ቃል ፡ ዕሩይ ። ወይፍታሕ ፡ በዘተማህደ ፡ እምቃል ፡ እሙን ፡ ውስተ ፡ መንበረ ፡ ፍትሕ ፡ ለእመ ፡ ተጠየቀ ፡ አእምሮቱ ፡ በኀቤሁ ፡ ወበኀበ ፡ ቀእማኒ ፡ እው ፡ በዘተከሥተ ፡ በሰማዕት ፡ ለእመ ፡ ቆመ ፡ እው ፡ መሐላ ፡ ለእመ ፡ ደለወ ፡ ወኢይፍታሕ ፡ ላዕለ ፡ ዘኢየአምሮ ፡ ዘእንበለ ፡ ግጻዌ ።

፩ሺ፩፻፶፪ ምዕራፍ ፡ ኃምስ ። በእንተ ፡ መሐላ ፡ ይቤ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ዕብ ፡ ፮፥ ፡ "ወመሐላስ ፡ ዘይምሕል ፡ በዐቢ ፡ በዘውእቱ ፡ የዐቢ ፡ እምኔሁ ፡ ይምሕል ፡ ወኵሉ ፡ ኃእዝ ፡ ዘትከውን ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ትትፌጸም ፡ በመሐላ ። ወበእንተ ፡ ውእቱ ፡ ፈድፋደ ፡ አፍቀረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ ያርኢ ፡ ለወራስያን ፡ ተስፋ ፡ ከመ ፡ ተስፋሁ ፡ ኢየዐሉ ፡ ወአጽንዖ ፡ በቃለ ፡ መሐላ" ። ወሶበ ፡ ኢዘሎ ፡ ምንትኒ ፡ ዘየዐቢ ፡ እምኔሁ ፡ ከመ ፡ ይምሐል ፡ ቦቱ ፡ መሐለ ፡ በርእሱ ፡ ወይቤ ፡ እን ፡ ባርኮ ፡ እባርከከ ፡ ወአብዝኆ ፡ አስተባዝኀከ ። ወቃለ ፡ እግዚእነ ፡ ዘውስተ ፡ ወንጌል ፡ ዘይቤ ፡ ኢትምሐሉ ፡ ግሙራ ፡ ወእኮ ፡ ዘይቤ ፡ በእንተ ፡ ተፋትሖተ ፡ አላ ፡ ይቤ ፡ በእንተ ፡ ተናግሮ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ፈጸመ ፡ ዘንተ ፡ ቃለ ፡ በቃሉ ፡ ዘይብል ፡ ለትኩን ፡ ቃልክሙ ፡ እመኒ ፡ እወ ፡ እወ ፡ ወእመኒ ፡ አልቦ ፡ አልቦ ። ወይቤ ፡ ካዕበ ፡ ዘተወሰከ ፡ ላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ እምእኩይ ፡ ውእቱ ። ወተወስኮሰ ፡ ይእቲ ፡ እንተ ፡ ኢይትፈቀድ ፡ ኀበ.ሃ ፡ ወከዊን ፡ መሐላስ ፡ በጊዜ ፡ ኃእዝ ፡ ናሁ ፡ ይትፈቀድ ፡ በበይነ ፡ ግብር ፡ ወባሕቱ ፡ ይደሉ ፡ ለሰብእ ፡ ከመ ፡ ኢይምሐል ፡ በዘይትከሀሎ ፡ ይቤሎ ፡ መሐላሁ ፡ በንዋዩ ፡ ወዘእንበለ ፡ ንዋዩ ፡ በእንተ ፡ ሰበየ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባሕቲቱ ፡ ወበእንተ ፡ ዘይሴፎ ፡ ዘሀሰወ ፡ ኀቤሁ ።

፩ሺ፩፻፶፫ ወይቤ ፡ ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ አፈወርቅ ፡ በውስተ ፡ ትርጓሜ ፡ ዝንቱ ፡ ቃል ፡ ወእመ ፡ ትቤ ፡ ምንት ፡ ይእቲ ፡ መሐላ ፡ እንተ ፡ የኀሥሣ ፡ ወይመጽእ ፡ ወይሁብ ፡ ሎቱ ፡ እምኔነ ፡ ለቢጹ ፡ በጊዜ ፡ ፈቀደ ፡ ኪያሃ ፡ እቤ ፡ በፈረሀ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይእቲ ። ወዘሂ ፡ ይገብር ፡ በሕገ ፡ ትእ

ስለ ፡ ዳኛ ።

በተሰበሰቡ ፡ በመጻሕፍት ፡ ትእዛዝ ፡ ወይም ፡ ለልቡናው ፡ በመሰለው ፡ ሕጋዊ ፡ ነገርን ፡ ካልለወጠ ፡ በቀር ፡ ወደማይጠቅም ፡ ነገር ፡ ከመተላለፍ ፡ ይልቅ ፡ ወደ ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ መመለስ ፡ ይሻላልና ፡ እወቅ ። በፍርድ ፡ አደባባይ ፡ ከታመነው ፡ ቃል ፡ የተነሣ ፡ በተገለጸለት ፡ ገንዘብ ፡ በእርሱና ፡ በታማኙ ፡ ዘንድ ፡ እውቀቱ ፡ ቢረጋገጥ ፡ ወይም ፡ በምስክሮቹ ፡ በተገለጸው ፡ ነገር ፡ ቢጸና ፡ ወይም ፡ መሐላ ፡ የሚገባው ፡ ቢሆን ፡ ይፍረድ ። በማያውቀውም ፡ ላይ ፡ ሳይለይ ፡ አይፍረድ ።

፩ሺ፩፻፶፪ ፭ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ ስለመሐላ ፡ ይናገራል ። ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ እንዲህ ፡ አለ ። ዕብ ፡ ፮ ። መሐላስ ፡ የሚምል ፡ ሰው ፡ ከእርሱ ፡ በሚበልጥ ፡ ይምላል ። በመካከላቸው ፡ የምትደረግ ፡ ክርክር ፡ ሁሉ ፡ በመሐላ ፡ ትፈጸማለች ። ስለዚህም ፡ ተስፋ ፡ ለሚወርሱ ፡ ተስፋውን ፡ እንዳይሰቀር ፡ ይገልጽ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጽሞ ፡ ወደደ ። በመሐላ ፡ ቃልም ፡ አጸናው ። ይምልበትም ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ የሚበልጥ ፡ ምንም ፡ ስለሌለ ፡ መባረክን ፡ እባርክሃለሁ ፡ መብዛትንም ፡ አበዛሃለሁ ፡ ብሎ ፡ በራሱ ፡ ማለ ። (ዕብ ፡ ፮ ፡ ፲፫ - ፲፬) ። ጌታችንም ፡ በወንጌል ፡ ከቶ ፡ አትማሉ ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ስለመፋረድ ፡ አይደለም ። ስለ መናገር ፡ ተናገረ ፡ እንጂ ። ይህንን ፡ ትእዛዝ ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ቃላችሁ ፡ እውነቱን ፡ እውነት ፡ ሐሰቱን ፡ ሐሰት ፡ ትሁን ፡ በሚል ፡ ቃሉ ፡ ፈጽሞታልና ። ዳግመኛም ፡ በዚህ ፡ ላይ ፡ የተጨመረውስ ፡ ከክፉ ፡ የተገኘ ፡ ነው ፡ አለ ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፴፬ - ፴፯) ። በእርሷ ፡ ላይ ፡ መጨመርስ ፡ የማትፈለግ ፡ ናት ። በክርክር ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ የመሐላ ሁኔታ ፡ በግልጽ ፡ ያስፈልጋል ። ነገር ፡ ግን ሰሰው ፡ መሐላውን ፡ በገንዘብ ፡ ወይም ፡ ያለገንዘብ ፡ ማስቀረት ፡ በሚቻለው ፡ ሁናቴ ፡ ስለእግዚአብሔር ፡ ግናናንት ፡ ብቻ ፡ በእርሱም ፡ ያለውን ፡ ተስፋ ፡ ስለሚያደርግ ፡ እንዳይምል ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፩፻፶፫ ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ አፈ ፡ ወርቅም ፡ ይህን ፡ ቃል በተረጐመበት ፡ አንቀጽ ፡ እንዲህ ፡ አለ ። መሐላ ፡ ምንድር ፡ ናት ? ፡ ብትል ፡ ከእኛ ፡ አንዱ ፡ በጓደኛው ፡ ላይ ፡ እርሷን ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ የሚሻት ፡ የሚያመጣት ፡ የሚሰጣት ፡ መሐላ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ ናት ፡ እላለሁ ። የመ

አንቀጽ ፡ ፶፫ ።

ዘዛት ፡ መሢሒሐውያት ፡ ኢያፈቅድ ፡ መሐላ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይከውን ፡ በኀበ ፡ ሰብእ ፡ ፍሩሀ ፡ ወእግዚአብሔር ፡ ይከውኖ ፡ ረዳኤ ።

፭ሺ፱፻፶፬ በስ ፡ ፪ቱ ፡ ኢትምሐል ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእንተ ፡ ግብር ፡ ዕሩቅ ፡ ወፈድፋደሰ ፡ በሐሰት ፡ ወናሁ ፡ አዘዘነ ፡ ከመ ፡ ኢንምሐል ፡ በካልእ ፡ እምትእዛዛተ ፡ መጻሕፍት ፡ እላ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ በግብር ፡ ንምሐል ፡ በእንተ ፡ ሕጸተ ፡ እእምሮቶሙ ፡ ለሰብእ ፡ ወእከ ፡ ዘእንበለ ፡ ፍርሀተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ ኢንትኩነን ፡ በመሐላ ፡ ዘምሉእ ፡ ፍርሀተ ። ዘ፷ወ፰ቱ ፡ ወእመበ ፡ እምኑልቈ ፡ ካህናት ፡ ዘይምሕል ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሐሰት ፡ ይሰደድ ፡ ፫ተ ፡ ዓመተ ፤

፭ሺ፱፻፶፭ መክ ፡ ፶ወ፰ቱ ፡ ፻፳ወ፯ቱ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ማእከለ ፡ ፪ቱ ፡ እደው ፡ ተሰናእዎት ፡ በተግባር ፡ እው ፡ ተሳትፎት ፡ እው ፡ ኪዳን ፡ ወጸሐፉ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ መጽሐፈ ፡ ጥዩቀ ፡ ለአጽንዖ ፡ መሐላ ፡ ዘማእከሌሆሙ ፡ ከመ ፡ ውትቶሙ ፡ ኢይገብኡ ፡ እምዘተሰነአዉ ፡ ቦቱ ። ወለእመ ፡ ገብአ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ እምነ ፡ ዘተጽሕፈ ፡ ይገሥጽ ፡ መኰንን ፡ በእንተ ፡ መሐላሁ ፡ በሐሰት ፡ ወይደልዎ ፡ ይግበር ፡ ዘሀለወ ፡ ጽሑፈ ፡ በመጽሐፍ ። መ፳ ፡ ፳ወ፩ዱ ፡ ወዘሂ ፡ ፈትሐ ፡ ላዕሌሁ ፡ መኰንን ፡ ከመ ፡ ይምሐል ፡ ወእንበረ ፡ እዴሁ ፡ ላዕለ ፡ ወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ ወመሐለ ፡ ቦቱ ፡ ወእምዝ ፡ ተከሥተ ፡ ሐሰቱ ፡ ይትገሠጽ ።

፭ሺ፱፻፶፮ ክፍል ፡ እእምር ፡ ከመ ፡ እምላካዊት ፡ ሕግ ፡ ናሁ ፡ ትፈቅድ ፡ ሥነ ፡ ምግባራት ፡ በእግዚእ ፡ ርትዕ ፡ በጥንተ ፡ ቀዳሚ ፡ ሕግ ፡ እምገቢ ፡ ቁሙር ፡ ግብራት ፡ ኀብእት ፡ ወገቢር ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ድኅረ ፡ ወንቀ ፡ ነበረ ፡ ተከልአ ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ብሊት ፡ እመሐላ ፡ በሐሰት ፡ ወከመ ፡ ይትገሠጽ ፡ ዘወድቀ ፡ ቦቱ ። ወመሐላሰ ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ሐዲስ ፡ በፍትሐ ፡ ልቡና ፡ ውእቱኬ ፡ ከመ ፡ ኢይንብቡ ፡ ቦቱ ፡ ግሙራ ፡ በእንተ ፡ ዘይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ "ተብሀለ ፡ ለቀደምትክሙ ፡ ኢትሕሰዉ ፡ ውስተ ፡ መሐላ ፡ ወአንሰ ፡ እብለክሙ ፡ ኢትምሐሉ ፡ ግሙራ" ።

ስለ ፡ ዳኞ ።

ሚሕን ፡ የትእዛዛት ፡ ሕግንም ፡ የሚሠራ ፡ መሐላን ፡ አይሻም ። እርሱ ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡ የተፈራ ይሆናልና ። እግዚአብሔርም ፡ ረዳት ፡ ይሆነዋልና

፭ሺ፱፻፶፬ በስ ፡ ፪ ። በተርታ ፡ ነገር ፡ ይልቁንም ፡ በሐሰት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ አትማል ። ከመጻሕፍትም ፡ ትእዛዝ ፡ ወጥተን ፡ በሌላ ፡ [illegible]ዳንምል ፡ እነሆ ፡ አዝዞናል ። በሰዎች ፡ እውቀት ፡ ማነስ ፡ በግድ ፡ እንድንምል ፡ ቢሆን ፡ ነው ፡ እንጂ ። ፍርሃትን ፡ በተመላ ፡ መሐላ ፡ እንዳይፈረድብንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያለመፍራት ፡ አይሁን ። ፷፰ ። ከካህናት ፡ ወገን ፡ በሐሰት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የማለ ፡ ቢኖር ፡ ፫ ፡ ዓመት ፡ ይለይ ።

፭ሺ፱፻፶፭ መክ ፡ ፶፰ ፡ ፻፳፯ ። በሁለት ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ የሥራ ፡ ስምምነት ፡ ወይም ፡ ሽርክነት ፡ ወይም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ቢኖር ፡ በመካከላቸውም ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለማጽናት እነርሱ ፡ ከተስማሙበት ፡ ውል ፡ እንዳይመለሱ ፡ የሚያረጋግጥ ፡ ደብዳቤ ፡ በመካከላቸው ፡ ቢጻፉ ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ ከተጻፈው ፡ ውል ፡ ቢመለስ ፡ በሐሰት ፡ ስለመማሉ ፡ ዳኛ ፡ ይቅጣው ። በመጽሐፍ ፡ ተጽፎ ፡ ያለውንም ፡ ያድርግ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። መ፳ ፡ ፳፩ ። ዳኛ ፡ እንዲምል ፡ የፈረደበትም ፡ ሰው ፡ እጁንም ፡ በቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ ላይ ፡ ጭኖ ፡ ቢምልበት ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሐሰቱ ፡ ቢገለጽ ፡ ይቀጣ ።

፭ሺ፱፻፶፮ ክፍል ። እነሆ ፡ የአምላክ ፡ ሕግ ፡ በመጀመሪያው ፡ ሕግ ፡ መሠረትነት ፡ ርትዕን ፡ በመግለጽ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ በተሠወረች ፡ ሥራ ፡ በመጽናት ፡ በኋለኛውም ፡ ሕግ ፡ በመሥራት ፡ የምግባራትን ፡ ደግነት ፡ እንደምትወድ ፡ እወቅ ። እነሆ ፡ በብሉይ ፡ ሕግም ፡ በሐሰት ፡ ከመማል ፡ መከልከል ፡ እንዲገባ ፡ የወደቀበትም ፡ እንዲቀጣ ፡ ተጽፏል ። (ዘዳ ፡ ፳ ፡ ፲፩) ። በሐዲስ ፡ ሕግ ፡ ግን ፡ በልቡና ፡ ፍርድ ፡ መሐላ ፡ ከቶ ፡ የማይናገሩት ፡ ነው ። ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ ለነበሩት ፡ ሰዎች ፡ በሐሰት ፡ አትማሉ ፡ የተባለውን ፡ ሰምታችኋል ። እኔ ፡ ግን ፡ ከቶ ፡ አትማሉ ፡ እላችኋለሁ ፡ ብሏል ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፴፫ - ፴፯)

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

፩ሺ፬፻፶፯ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ በግብር ፡ አው ፡ ዘእንበለ ፡ ግብር ፡ እመ ፡ አኮ ፡ ለእመ ፡ ይከውን ፡ ዘተብሀለ ፡ በአእምሮ ፡ ወአስተማስሎ ፡ በእንተ ፡ ዘተብህለ ፡ ቀዳሚ ፡ ይኩን ፡ ከማሁ ። ወዳግማዊኒ ፡ ወውእቱ ፡ መሐላ ፡ ዘይከውን ፡ ውስተ ፡ ቃላት ፡ ላዕለ ፡ ፍናተ ፡ ስሒት ፡ መርስዐት ፡ በእንተ ፡ እከዩ ፡ ዘልማድ ፡ ዘከመ ፡ ወጺቅ ፡ ውስተ ካልአት ፡ ግብራት ፡ በአእምሮ ፡ ወዘእንበለ ፡ አእምሮ ፡ ወፈድፋደሰ ፡ ዘእንበለ ፡ ተሐዝቦ ፡ እንዘ ፡ ኢይፈቅድ ፡ ይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ንስሐ ፡ ለእመኒ ፡ መሐለ ፡ በጽድቅ ፡ አው ፡ በሐሰት ።

፩ሺ፬፻፶፰ ወቀዳሚስ ፡ እመኒ ፡ ቦ ፡ ከመ ፡ ይትመሰል ፡ በመሐላ ፡ ዘመን ፡ ዘኀለፈ ፡ ወበዘይመስሎ ፡ ዘውእቱ ፡ እግዚአብሔርሃ ፡ ከመ ፡ ኢገበርኩ ፡ አው ፡ ገበርኩ ፡ አው ፡ አልቦቱ ፡ ኀቤየ ፡ አው ፡ ሊተ ፡ ኀቤከ ። ወእመአኮ ፡ ለእመ ፡ ይትሜሰል ፡ በዘመን ፡ ዘይመጽእ ፡ ወእምሳሊሁ ፡ የአምር ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ ኢይገብር ፡ ወእመኒ ፡ እገብር ። ተመስሎሰ ፡ በኀላፊ ፡ ይትከፈል ፡ ኀበ ፡ ፫ቱ ፡ አክፋል ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ምስለ ፡ አእምሮ ፡ ጥዩቀ ፡ እንዘ ፡ ሕሊናሁ ፡ የኀብር ፡ ምስለ ፡ ቃሉ ፡ ወለዘንቱሰ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይቤዝውዎ ፡ በዕርቅ ፡ ለእመ ፡ ተከሀለ ። ወለእመ ፡ ኢተከሀለ ፡ ይከውን ፡ ጌጋዩ ፡ ላዕለ ፡ ዘአምሐሎ ፡ ለእመ ፡ አእመረ ፡ ግዕዞ ፡ ዚአሁ ፡ ወሕሊናሁ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘኢተዓቀበ ፡ ለዘሳዐሎሁ ፡ ግብር ፡ ውስተ ፡ ነፍሱ ፡ ለእመ ፡ አእመረ ፡ መሐለ ፡ ዘውእቱ ፡ ይለም ፡ ኀቤሁ ፡ ኀበ ፡ አሚን ፡ ወአስተዖርዮ ፡ እምእግዚአብሔር ፡ ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ ዘየኀብር ፡ ስሀልዎ ፡ ኢይደልዎ ፡ ዕዳ ፡ ምንትኒ ፡ ዘእንበለ ፡ ዘይትሐዘብ ፡ ሎቱ ፡ ሕሊናሁ ።

፩ሺ፬፻፶፱ ወዳግማዊትኒ ፡ ለእመ ፡ ይከውን ፡ ምስለ ፡ አእምሮ ፡ ሐሰት ፡ ወውእቱ ፡ ዕልወት ፡ ቀል ፡ እምሕሊና ። ወዝንቱ ፡ ይደሉ ፡ ኀዲጎቱ ፡ ሎቱ ፡ በእንተ ፡ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በውስተ ፡ አሪት ፡ ዘይብል ፡ ኢትምሐል ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪከ ፡ በሐሰት ፡ ወለእመ ፡ ወድቀ ፡ በውእቱ ፡ እምሰይጣን ፡ ይደልዎ ፡ ግብአ ፡ እምኔሁ ፡ ኀበ ፡ አሚን ፡ ወእምዝ ፡ ኀበ ፡ ንስሐ ።

፩ሺ፬፻፷ ወሣልሰቲኒ ፡ ለእመ ፡ ይከውን ፡ ምስለ ፡ ስሒት ፡ ወዝንቲኒ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይትቤዘው ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

፩ሺ፬፻፶፯ በግድ ፡ ወይም ፡ ያለግድ ፡ ቢሆን ፡ ያም ፡ ባይሆን ፡ የተባለው ፡ ነገር ፡ በዕውቀት ፡ ወይም ፡ በማስመሰል ፡ ቢሆን ፡ መጀመሪያ ፡ ስለተነገረ ፡ እንደዚያው ፡ ይሁን ። ሁለተኛውም ፡ በመሳትና በመርሳት ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ስለልማድ ፡ ከፋት በቃል ፡ የሚሆን ፡ መሐላ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በዕውቀት ፡ በአለማወቅም ፡ ቢሆን ፡ በሌሎች ፡ ሥራዎች ፡ እንደ ፡ መውደቅ ፡ ያለ ፡ ነው ። ይልቁንም ፡ ያለጥርጥር ፡ ሳይወድ ፡ በእውነት ፡ ወይም ፡ በሐሰት ፡ ቢምል ፡ ለእርሱ ፡ ንስሓ ይገባዋል ።

፩ሺ፬፻፶፰ መጀመሪያ ፡ ግን ፡ ባለፈው ፡ ዘመን ፡ መሐላ ፡ በሚመስለውም ፡ ይመስል ፡ ዘንድ ፡ ቢኖር ፡ ይኸውም ፡ እንዳላደረግሁ ፡ ወይም ፡ እንዳደረግሁ ፡ ወይም ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ገንዘብ ፡ እንዳለህ ፡ ወይም ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ገንዘብ ፡ እንዳለኝ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማለት ፡ ነው ። ያም ፡ ባይሆን ፡ በሚመጣው ፡ ዘመን ፡ በሚመስለውም ፡ ቢመስል ፡ እንዳላደርገው ፡ ወይም ፡ እንዳደርገው ፡ እግዚአብሔር ፡ ያውቃል ፡ ማለት ፡ ነው። ባለፈው ፡ መመስልስ ፡ በ፫ ፡ ይከፈላል ። ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ ሐሳቡ ፡ ከቃሉ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ሁኖ ፡ በዕውቀት ፡ እርግጠኛ ፡ ቢሆን ፡ እንዲህ ፡ ያለውን ፡ ቢቻል ፤ በዕርቅ ፡ ሊያድኑት ፡ ይገባል ። ባይቻል ፡ ግን ፡ በደሉ ፡ በማለው ፡ ላይ ፡ ይሆናል ። በደሉንም ፡ ቢያውቅ ፡ ሐሳቡም ፡ በሥራው ፡ ለራሱ ፡ የማይጠበቅ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ይህንን ፡ ቢያውቅ ፡ ወደ ፡ ማመንና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ወደሚገኝ ፡ ይቅርታ ፡ መመለስ ፡ ተገባው ። ለመኖር ፡ የሚስማማ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ዕዳ ፡ አይገባውም ። ሕሊናው የሚጠራጠርበት ፡ ካልሆን ፡ በቀር ።

፩ሺ፬፻፶፱ ሁለተኛይቱም ፡ ሐሰት ፡ ከዕውቀት ፡ ጋራ ፡ ቢሆን ፡ ያህም ፡ ከሐሳብ ፡ የተነጣ ፡ የቃል ፡ ሽንገላ ፡ ነው ። ይህንም ፡ ሊተዉት ፡ ይገባል ። እግዚአብሔር ፡ በኦሪት ፡ በፈጣሪህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ በሐሰት ፡ አትማል ፡ ብሎ ፡ ስለተናገረ ፡ (ዘጸ ፡ ፳ ፡ ፲፩) ። ከሰይጣን ፡ የተነሣ ፡ በመታወክ ፡ ቢወድቅ ፡ (ቢምል) ፡ ከዚህ ፡ ወደ ማመን ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ንስሐ ፡ መመለስ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፬፻፷ ፫ኛይቱም ፡ በስሕተት ፡ ቢሆን ፡ ያህም ፡ በሚታገሡበት ፡ አስቀድመን ፡ ከተናገርነው ፡

ብርሃን ፡ ዘይትዔገሥ ፡ ቦቱ ፡ ወዘይበዝኅ ፡ እም
ውንዮ ፡ ዘአቅደምን ፡ ዘከሮቱ ፡ ወለእመ ፡ ኢተ
ከሀለ ፡ ጉጋዩ ፡ ላዕለ ፡ አምሐሊ ፡ ለእመ ፡ አእ
መረ ፡ ግፍዖ ፡ እሙ ፡ ተስሕተ ፡ ውስቴቱ ። ወጥ
ዩቅስ ፡ በዘይመጽእ ፡ እስመ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡
ጽድቅ ፡ ውስቴቱ ፡ ዘኢይከውን ፡ አበሳ ፡ ይለወ
እኒዞቱ ፡ ሎቱ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ አበሳ ፡ ይፀውር
ይለወ ፡ ገቢእ ፡ እምኔሁ ፡ ወተመስሎስ ፡ በዘይ
መጽእ ፡ ለእመ ፡ አልቦቱ ፡ ቃል ፡ እሙን ፡ ኢይ
ደሉ ፡ ዘእንበለ ፡ ከመ ፡ ይፀመዱ ፡ ኪያሁ ። ወእ
መሰ ፡ ቦቱ ፡ እሙን ፡ ቃል ፡ ደለዎ ፡ ከመ ፡ ይኅ
ድግዎ ፡ ወንስሓስ ፡ ለዘከማሁ ፡ ከመ ፡ ኢይወ
ስኩ ፡ ዲበ ፡ አበሳሁ ፡ በቃል ፡ ኃጢአተ ፡ ዘገቢር

፩ሺ፬፻፹፩ አእምር ፡ ከመ ፡ ቃለ ፡ መሐላ ፡ ውእቱ ፡
መሐላ ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወአልቦ ፡ ፍል
ጠት ፡ ማእከለ ፡ እሉ ፡ ቋቱ ፡ ማእከለ ፡ ስመ ፡
እግዚአብሔር ፡ ወስመ ፡ ክርስቶስ ፡ እስመ ፡
ኵሉ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እምነ ፡ እሉ ፡ ቋቱ ፡ አስማት ፡
ስመ ፡ እምላክ ፡ ውእቱ ፡ ስመ ፡ ክርስቶስ ፡ እም
ላክ ፡ ውእቱ ፡ ዘተሰብአ ። ወለዘፈቀደ ፡ ይትሉ ፡
ዘንተ ፡ ለተገርዋ ፡ ወለእፍርሆ ፡ በምንትኒ ፡
እምአስማቲሁ ፡ እለ ፡ ዝኩራት ፡ በመጻሕፍት ፡
እምላካውያን ፡ ይከውኖ ፡ ሎቱ ፡ ውእቱ ፡
በእምሳል ፡ ከመ ፡ ዘይብል ፡ እግዚአብሔር ፡
ዐቢይ ፡ ወኀያል ፡ ከሃሊ ፡ ማእምር ፡ ዘንቡእ ፡
ወዘገሃድ ፡ ዘይፈድዮ ፡ ለኵሉ ፡ ለለ፩ዱ ፡ በከመ፡
ምግባሩ ፡ ዘኢያነጽሖ ፡ ለዘመሐለ ፡ ስሞ ፡ በሐ
ሰት ፡ ወመሐላስ ፡ ዘእንበለ ፡ በእንግዚአብሔር ፡
ወበንገሬቱሁ ፡ ወበእሊእሁ ፡ ኢይደሉ ፡ ወእሊ
እሁስ ፡ ዘከመ ፡ ወንጌል ፡ ወመስቀል ፡ ወታ
ቦቱ ፡ ወቅዱሳኒሁ ። ወኢይደሉ ፡ እምሕሎቱ
ለዘጠፍአ ፡ ልቡ ፡ ወለዘኢያብጽሖ ፡ እካለ ፡
መጠን ።

፩ሺ፬፻፹፪ ሥርዋጽ ፡ ወለዝንቱ ፡ ቃል ፡ ቦቱ ፡ ኅሠሣ ፡
እስመ ፡ መሐላ ፡ ዘበእግዚአብሔር ፡ ይከውን ፡
እምኔሁ ፡ መሐላ ፡ በክርስቶስ ፡ ወኢይትዌለጥ ፡
እስመ ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሎቱ ፡ በብሒት ፡
ይትበሀል ፡ ኀበ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡
ቅዱስ ፡ ወስመ ፡ ክርስቶስኒ ፡ ይትበሀል ፡ ኀበ ፡
ስመ ፡ ወልድ ፡ ባሕቲቱ ።

፩ሺ፬፻፹፫ ምስራፍ ፡ ፮ቱ ፡ በእንተ ፡ መንበረ ፡ ፍትሕ ፡

ከደግ ፡ ነገር ፡ ወገን ፡ በሚበዛ ፡ ዕርቅ ፡ ሊበኸር ፡
ይገባል ። ባይቻል ፡ ግን ፡ በደሉ ፡ በአማዩ ፡ ላይ፡
ነው ። በደሉን ፡ ቢያውቅ ፡ ወይም ፡ በውስጡ ፡
ቢሳሳት ። እርግጠኛውስ ፡ በሚመጣው ፡ ነው ።
በውስጡ ፡ በደል ፡ የማይሆን ፡ እውነት ፡ ቢሆን፡
እርሱን ፡ መያዝ ፡ ይገባናልና ። በደሉን ፡ የሚሸ
ከም ፡ ቢሆንም ፡ ከእርሱ ፡ መመለስ ፡ ተገባ ።
በሚመጣውም ፡ መምሰል ፡ የታመነ ፡ ቃል ፡
ባይኖረው ፡ ሊያፈርሱት ፡ እንጂ ፡ ሊፈጽሙት ፡
አይገባም ። እውነት ፡ ቃል ፡ ቢኖርበት ፡ ግን ፡
ሊተዉት ፡ ተገባ ። ንስሓም ፡ ለእንደዚህ ፡ ያለ ፡
ነው ። በነቢብ ፡ ኃጢአት ፡ ላይ ፡ የገቢር ፡ ኃጢ
አት ፡ እንዳይጨምር ።

፩ሺ፬፻፹፩ የመሐላ ፡ ቃል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
መማል ፡ እንደሆነ ፡ እወቅ ። በእግዚአብሔር ፡
ስምና ፡ በክርስቶስ ፡ ስም ፡ በእኒህ ፡ በሁለቱ ፡
መካከል ፡ ልዩነት ፡ የለም ። ከእኒህ ፡ ከሁለቱ ፡
ስሞች ፡ ሁሉ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ የእምላክ ፡ ስም ፡
ነውና ። ክርስቶስ ፡ የሚለው ፡ ስም ፡ ሰው ፡
የሆነ ፡ እምላክ ፡ ነው ። ለማስፈራራትና ፡ ለማስ
ገረም ፡ በቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ፡ ከተነገሩት ፡
ስሞቹ ፡ በማናቸውም ፡ ይህን ፡ ሊከታተል ፡
ቢወድ ፡ ለእርሱ ፡ ይገባዋል ። ለምሳሌ ፡ ታናና ፡
ኀያል ፡ ሁሉን ፡ ቻይ ፡ የተሰወረውንና ፡ የተገለ
ጸውን ፡ የሚያውቅ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ እንደ ፡
ሥራው ፡ የሚከፍል ፡ በሐሰት ፡ በስሙ ፡ የማለ
ውን ፡ የማያነፃ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይወቅብኝ
እንደማለት ፡ ነው ። መሐላም ፡ በእግዚአብሔር፡
በነገሮቹና ፡ በወገኖቹ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አይገ
ባም ። ወገኖቹም ፡ እንደ ፡ ወንጌል ፡ እንደ ፡
መስቀሉና ፡ እንደ ፡ ታቦቱ ፡ እንደ ፡ ቅዱሳኖ
ቹም ፡ ያሉት ፡ ናቸው ። አእምሮዉ ፡ የጠፋ
ውንና ፡ እካለ ፡ መጠን ፡ ያላደረሰውን ፡ ማማል ፡
አይገባም ።

፩ሺ፬፻፹፪ ሥርዋጽ ። በዚህ ፡ ቃል ፡ ምርምር ፡ አለበት ።
በእግዚአብሔር ፡ የተማለው ፡ መሐላ ፡ ከእርሱ ፡
የተነሣ ፡ በክርስቶስ ፡ መማል ፡ ይሆናልና ።
አይለወጥምም ። ክብር ፡ ይግባውና ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የሚለው ፡ ስም ፡ ስአብ ፡ ለወልድ ፡ ለመ
ንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ይነገራልና ። ክርስቶስ ፡ የሚ
ለውም ፡ ስም ፡ ለወልድ ፡ ስም ፡ ብቻ ፡ ይነገ
ራል ።

፩ሺ፬፻፹፫ ፮ኛው ፡ ምስራፍ ፡ ስለፍርድ ፡ አደባባይ ፡

ወእለ ፡ ይበጽሑ ፡ ኀቤሁ ፡ ወእለኒ ፡ ኢይበጽሑ ድስቅ ፡ ፲፡ ፡ ለየሀልዉ ፡ ምስሌክሙ ፡ ኤጲስ ቆጶሳት ፡ በመንበረ ፡ ፍትሕ ፡ ቀሳውስት ፡ ወዲ ያቆናት ፡ ወፍትሑ ፡ ዘእንበለ ፡ አድልዎ ፡ በር ትዕ ፡ ከመ ፡ ሰብአ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወእእምሩ፡ ከመ ፡ ክርስቶስ ፡ ወልደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሀልው ፡ ውእቱ ፡ ምስሌክሙ ፡ በሀውደ ፡ ፍትሕ ፡ ከመ ፡ ይርአይ ፡ ዘትፌትሑ ፡ ቦቱ ፡ ወይሰማዕ ፡ ዘትትናገሩ ፡ ቦቱ ፡ ወናሁ ፡ ይቤ ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ኢትኅበር ፡ ምስለ ፡ ብዙኃን ለገቢረ ፡ እከይ ፡ ወኢትትወከፍ ፡ ነገረ ፡ ፅሩዐ ፡ ወኢትንበር ፡ ውስተ ፡ ማኅበርሙ ፡ ለእለ ፡ ያፀ ርዑ ፡ ጽድቀ ።

፩ሺ፬፻፳፬ ክፍል ፡ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ያስተዳልዉ ፡ ለፈ ታሕት ፡ ምንባረ ፡ ንጹሐ ፡ ወጽሩየ ፡ ኀበ ፡ ኢይ ለክፎሙ ፡ ቍር ፡ ወኢሐሩር ፡ ወእጺእት ፡ በውስቴታ ፡ ወኢይንበሩ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስ ቲያን ፡ በምሥዋዕ ፡ ለፈቲሐ ፡ ፍትሕ ፡ እስመ ፡ በዋእ ፡ ኀበ ፡ ምሥዋዕ ፡ ኢብውሕ ፡ ዘእንበለ ፡ ለካህናት ፡ ከመ ፡ ይባኡ ፡ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ውስቴቱ ፡ ተባእሶ ፡ ወክሳሕ ።
ወመፍትው ፡ ከመ ፡ የሀልዉ ፡ ኀቤሁ ፡ ማእም ራን ፡ ወእለ ፡ ይከውኑ ፡ ስምዐ ፡ ከመ ፡ ሶበ ፡ ተዳደቀ ፡ ጠዋይ ፡ ነገር ፡ ከመ ፡ ይትማከር ፡ ምስሌሆሙ ፡ በእንቲአሁ ። ወለእመኒ ፡ ኢተ ጠየቀ ፡ ፈቲሐ ፡ ፍትሕ ፡ ያስተድኀር ፡ ኪያሁ ፡ እስከ ፡ ይጤየቅ ።

፩ሺ፬፻፳፭ ምስራፍ ፡ ፯፡ ። በእንተ ፡ ጊዜያተ ፡ ፍትሕ ፡ ወከዋኒሁ ። መ፲ ፡ ፶ ፡ ኢይሥርዑ ፡ መኳንንት ፡ በምንትኒ ፡ እምሥርዓታቲሆሙ ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡ ወኢያፍርሁ ፡ በውስቴቱ ፡ ሰብአ ፡ ኢ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ ወኢ ፡ መኰንን ፡ ወኢ ፡ ሐራ ፡ ወኢ ፡ መጸብሕዊ ።

፩ሺ፬፻፳፮ ድስቅ ፡ ፲፡ ፡ ወይኩን ፡ ተጋብኦትክሙ ፡ በእንተ ፡ ፍትሕክሙ ፡ እምዕለተ ፡ ሰኑይ ፡ ወለ እመ ፡ ሀለወ ፡ ሀየ ፡ ተጋእዞ ፡ ፍልጡ ፡ ኪያሃ ፡ ወኩኑ ፡ ዕሩቃነ ፡ በዝንቱ ፡ ኑኃ ፡ ይእቲ ፡ ሰሙን ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ሰንበት ፡ ከመ ፡ ትትፌ ጸም ፡ ነገረ ፡ ተባእሶ ። ወበዕለተ ፡ እሑድ ፡ ቅድ ስት ፡ ትከውኑ ፡ እንከ ፡ ዘናሁ ፡ አስተሳለም ክሙ ፡ ማእከለ ፡ ተጻባእያን ፡ ወእምከመ ፡ በጽሑ ፡ ኀቤክሙ ፡ ተጻላእያን ፡ ይቁሙ ፡ ክል ኤሆሙ ፡ በቅድሜክሙ ፡ ማእከለ ፡ መንበረ ፡



ወደእርሱ ፡ ስለሚደርሱና ፡ ስለማይደርሱ ፡ ይና ገራል ። ድስቅ ፡ ፲ ። ኤጲስቆጶሳት ፡ ሆይ ፡ ከፍ ርድ ፡ ሸንጎ ፡ ቀሳውስትና ፡ ዲያቆናት ፡ ከእና ንተ ፡ ጋር ፡ ይኑሩ ። የእግዚአብሔርም ፡ ሰዎች ፡ እንደመሆናችሁ ፡ ያለ፡ አድልዎ ፡ በእውነት ፡ ፍረዱ ። የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ክርስቶስ ፡ የምትፈርዱትን ፡ ሊያይ ፡ የምትናገሩትንም ሊሰማ ፡ በፍርድ ፡ አደባባይ ፡ ከናንተ ፡ ጋር ፡ እንዳለ ፡ እወቁ ። እነሆ ፡ በመጽሐፍ ፡ ክፋትን ፡ ለመሥራት ፡ ከብዙዎች ፡ ጋራ ፡ አትተባበር ፡ የማይረባ ፡ ነገርንም ፡ አትቀበል ፡ እውነትን ፡ በማይናገሩ ፡ ሰዎች ፡ ስብሰባ ፡ ውስጥም ፡ አት ቀመጥ ፡ ተብሏል ። (ዘፀ ፡ ፳፫ ፡ ፲፪) ።

፩ሺ፬፻፳፬ ክፍል ፡ ብርድና ፡ ሐሩር ፡ ክፉ ፡ ሽታም ፡ ከማያገኛቸው ፡ ንጹሕና ፡ ጥሩ ፡ መቀመጫ ፡ ለዳኞች ፡ ሊያዘጋጁ ፡ ይገባል ። በሚሠዋበት በቤተክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ ፍርድ ፡ ለመፍረድ ፡ አይቀመጡ ። ወደ ፡ ምሥዋዕ ፡ መግባት ፡ ከካህ ናት ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ አይገባ ምና ። ጠብና ፡ ጩኸት ፡ በውስጡ ፡ ሊሆን ፡ አይገባም ። አዋቂዎችና ፡ ምስክር ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ጠማማ ፡ ነገር ፡ ባጋጠመው ፡ ጊዜ ፡ ስለእርሱ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እንዲማከር ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ሊኖሩ ፡ ይገባል ። ፍርዱም ፡ ያልተረዳው ፡ ቢሆን ፡ እስኪረዳው ፡ ድረስ ፡ ያቆይ ።

፩ሺ፬፻፳፭ ሰባተኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ስለፍርድ ፡ ጊዜያትና ፡ ስለሁኔታው ፡ ይናገራል ። መ፲ ፡ ፶ ። መኳንንት በዕለተ ፡ እሑድ ፡ ከሥርዓታቸው ፡ ወገን ፡ ምን ንም ፡ አይሥሩ ። በዚያም ፡ (በእሑድ ፡ ቀን) ፡ አበዳሪና ፡ ዳኛ ፡ ቀፍፋሪና ፡ ቀራጭም ፡ ሰውን ፡ አያስፈሩሩ ።

፩ሺ፬፻፳፮ ድስቅ ፡ ፲ ። ስለፍርዳችሁ ፡ መሰብሰባችሁ ፡ ከሰኞ ፡ ጀምሮ ፡ ይሁን ። ከዚያም ፡ ክርክር ፡ ቢኖ ር ፡ እርሱን ፡ ለዩ ። በዚህ ፡ በዚህች ፡ ሳምንት ፡ ርዝመትም ፡ እስከ ፡ ቅዳሜ ፡ ድረስ ፡ ከነገር ፡ ተለዩ ። የጠብ ፡ ነገር ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ። በከበ ረች ፡ በዕለተ ፡ እሑድም ፡ እነሆ ፡ በተጣሉት ፡ መካከል ፡ አስታራቂዎች ፡ ትሆናላችሁ ። የተጣ ሉ ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ቢደርሱ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ባህል ፡ በፍርድ ፡ ሸንጎ ፡ መካከል ፡ ሁለ ቱም ፡ በፊታችሁ ፡ ይቁሙ ። የጥላቸውንም ፡

አንቀጽ ፡ ፶፫ ።

ፍትሕ ፡ ከመ ፡ ባህለ ፡ ሕግ ፡ ወእምከመ ፡ ሰማዕክሙ ፡ ቃለ ፡ ተጻልአተሙ ፡ ፍትሑ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ በጽድቅ ፡ ወበርትዕ ፡ ወኢትፍትሑ ፡ በቃለ ፡ ፩ዱ ፡ ሰድው ፡ ዘእንበለ ፡ ይብጻሕ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ እላ ፡ ሶበ ፡ ይትራከቡ ፡ ፪ሆሙ ፡ ተጻላእያን ፡ ፍትሑ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ በርትዕ ። ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኅሥሥዋ ፡ ለጽድቅ ፡ ወፍትሑ ፡ ባቲ ፡ ወሶበ ፡ ትነብሩ ፡ ለኰንኖ ፡ እንዘ ፡ ተጻላእያን ፡ ይትኳነኑ ፡ በቅድሜክሙ ፡ ገጸ ፡ በገጽ ፡ ኢትስምይዎሙ ፡ አኃወ ፡ እስከ ፡ ይትገብሩ ፡ ዕርቀ ፡ ወሥርዐቶ ፡ ዕዳሆሙ ፡ በጽድቅ ።

፩ሺ.፪፻፳፯ ወናሁ ፡ ንቤ ፡ ከመ ፡ ኢይደሉ ፡ ትፍትሑ ፡ ላዕለ ፡ ፩ዱ ፡ ዘእንበለ ፡ ይብጽሑ ፡ ፪ኤሆሙ ፡ ኅቡረ ፡ እስመ ፡ አንትሙ ፡ ለእመ ፡ ሰማዕክሙ ፡ ቃለ ፡ ፩ዱ ፡ መቅሰተ ፡ ዚአሁ ፡ ወፈታሕክሙ ፡ ፍቱን ፡ እንዘ ፡ ኢሀለወ ፡ ካልኡ ፡ ምስሌክሙ ፡ ከመ ፡ ያውሥእ ፡ በእንተ ፡ ንፍሱ ፡ ትከውኑ ፡ አንትሙ ፡ ድልዋነ ፡ ለኵነኔ ፡ ዘፈታሕክሙ ፡ ቦቱ ፡ ወትከውኑ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አኃዜ ፡ ኵሉ ፡ ሱታፌሁ ፡ ለሐሰት ፡ ወመከፈልቱ ፡ ዚአሃ ።

፩ሺ.፪፻፳፰ መከ ፡ ፳ወ፱ቱ ፡ ኢይደልዎ ፡ ለብእሲ ፡ ከመ፡ ይረሲ ፡ ግብረ ፡ ህየንቴሁ ፡ በእንተ ፡ ተዋቅሶ ፡ ቅስት ፡ በኀበ ፡ ፈታሒ ፡ እስመ ፡ ኢይትዔረይ ፡ በክብር ፡ ምስለ ፡ እግእዚ ፡ ገብር ።

፩ሺ.፪፻፳፱ ክፍል ፡ ፩ዱ ፡ ወአእምሮ ፡ ከመ ፡ እምጽኦ ፡ ስማዕት ፡ ለጥያቄ ፡ ላዕለ ፡ ዘይሰኪ ፡ መመሐላሰ ላዕለ ፡ ዘይክሕድ ። ወለእመ ፡ ተማመሩ ፡ በመ [redacted] ፡ ላዕለ ፡ ዘይሰኪ ፡ ዝኒ ፡ ይከውን ፡ ወይትገብእ ፡ ዕዳ ፡ ላዕለ ፡ ዘክሕደ ፡ ኪያሁ ፡ እስመ ፡ ሰካዪ ፡ ለሊሁ ፡ ኅማሚሁ ፡ ውእቱ ፡ ወዘይሰከይዎሂ ፡ ለሊሁ ፡ ዘይትኀሠሥ ፡ እምኔሁ ። መስከየ ትሰ ፡ ኢይከውን ፡ ዘእንበለ ፡ በዘውእቱ ብዉሕ ፡ ላዕለ ፡ እስተዋፅኦቱ ፡ ለዘይሰኪ ፡ በእንቲአሁ ፡ በከመ ፡ ብዉሕ ፡ ላዕለ ፡ እስተዋፅኦቱ ፡ ውእቱ ፡ ዘይሰክይዎ ፡ ቦቱ ፡ በእንቲአሁ ።

፩ሺ.፪፻፴ ወእምከመ ፡ በጽሑ ፡ ፪ኤሆሙ ፡ ተጻላእያን ለተፋትሖ ፡ ይበሎሙ ፡ ፈታሒ ፡ በሉ ፡ ተናገሩ ፡ ወለሊሁኒ ፡ ያርምም ፡ እስከ ፡ ይትናገሩ ። ወለእመ ፡ ሰከዩ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይቅድም ፡ ዘሰከየ ፡ አቅዲሙ ፡ ወእምከመ ፡ ፈጸመ ፡ ነገረ ፡ ቅስቱ ፡ ይስምዑ ፡ ቅስተ ፡ ካልኡ ። ወለእመ ፡ ኀሰ ፡ ፩ዱ ፡ በነገር ፡ ለካልኡ ፡ አው

ስለ ፡ ዳኛ ።

ነገር ፡ ከሰማችሁ ፡ በኋላ ፡ በመካከላቸው ፡ በእውነትና ፡ በቅን ፡ ፍረዱ ። ባላጋራው ፡ ሳይመጣ በ፩ ፡ ባላጋራ ፡ ቃል ፡ አትፍረዱ ። ሁለቱ ፡ ተከራካሪዎች ፡ በተገናኙ ፡ ጊዜ ፡ በመካከላቸው በቅን ፡ ፍረዱ ፡ እንጂ ። እግዚአብሔር ፡ ጽድቅን (እውነት) ፡ ፈልጉት ፡ በእርሷም ፡ ፍረዱ ፡ ብሏል ። (ኢሳ ፡ ፩ ፡ ፲፯) ። የተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ በፊታችሁ ፡ ሲከራከሩ ፡ ለፍርድ ፡ በተቀመጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ እስኪታረቁ ፡ ድረስ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ወንድሞች፡ አትበሏቸው ። ዕዳቸውንም ፡ በእውነት ፡ ይቅር በሏቸው ።

፩ሺ.፪፻፳፯ እነሆ ፡ ሁለቱም ፡ በአንድነት ፡ ሳይቀርቡ ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ ልትፈርዱ ፡ እንዳይገባ ፡ ተናገርን ። ሌላው ፡ በስራሱ ፡ መልስ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ሳይኖር ፡ የአንዱን ፡ ቃልና ፡ ክርክሩን ፡ ሰምታችሁ ፡ ፈጥናችሁ ፡ ብትፈርዱ ፡ በፈረዳችሁበት ፡ ፍርድ ፡ ለመቀጣት ፡ እናንተ ፡ ዝግጁዎች ፡ ትሆናላችሁና ። ሁሉን ፡ በያዘ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የሐሰት ፡ ተባባሪዎችና፡ የእርሷ ፡ ዕድል ፡ ፈንታ ፡ ትሆናላችሁ ።

፩ሺ.፪፻፳፰ መከ ፡ ፳፱ ። ለሰው ፡ በዳኛ ፡ ዘንድ ፡ ስለጠቡ ክርክር ፡ ባሪያውን ፡ ነገረ ፡ ፈጅ ፡ ሊያደርግ ፡ አይገባውም ። ባሪያ ፡ በክብር ፡ ከጌታው ፡ ጋር ፡ አይተካከልምና ።

፩ሺ.፪፻፳፱ ክፍል ፡ ፩ ። የማስረጃ ፡ ምስክር ፡ ማምጣት ፡ ለከሳሽ ፡ እንደሆነ ፡ እወቅ ። መሐላ ፡ ግን ፡ ለሚክድ ፡ ነው ፡ በከሳሽ ፡ ላይ ፡ በመሐላው ፡ ቢስማሙ ፡ ይህም ፡ ይሆናል ። ዕዳም ፡ እርሱን ፡ወደ፡ ካደ ፡ ይመለሳል ። ከሳሽ ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ፈላጊው ፡ ነውና ፡ ተከሳሽ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ የሚፈለግበት ፡ ነውና ። ስለእርሱ ፡ የከሰሱትም ፡ ሰው፡ በማውጣጣቱ ፡ ላይ ፡ እንደሚገባው ፡ ክስ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ የተከሰሰበትን ፡ ለማውጣጣት ፡ ሥልጣን ፡ ባለው ፡ ላይ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አይሆንም ።

፩ሺ.፪፻፴ ሁለቱ ፡ ተከራካሪዎች ፡ ለመፋረድ ፡ ከቀረቡ ፡ ዳኛው ፡ በሉ ፡ ተናገሩ ፡ ይበላቸው ። እርሱም ፡ እስኪናገሩ ፡ ድረስ ፡ ዝም ፡ ይበል ። ከእነርሱም ፡ እያንዳንዱ ፡ ቢካሰስ ፡ አስቀድሞ ፡ የከሰሰው ፡ ይቅደም ። (ከሳሽ) ፡ የጠቡን ፡ ነገር ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ፡ የሌላውን ፡ (የተካሳሹን) ፡ ክርክር ፡ ይስሙ ። አንዱ ፡ ሌላውን ፡ በነገር ፡ ቢነካው ፡

አንቀጽ ፡ ፺፫ ።

አውዕአ ፡ ቃለ ፡ ሕሡመ ፡ ይክልእ ፡ ወለእመ ፡ ደገመ ፡ ይገሥጽ ፡ ወእመኒ ፡ ወሰከ ፡ ያውግዝ ።

፩ሺ.፬፻፸፩ ወዘሂ ፡ ሰከየ ፡ ግብረ ፡ ዘኢይትሌበው ፡ ይበሎ ፡ አጠይቅ ፡ ነገረከ ፡ ዘሰከይከ ፡ በእንቲአሁ ። ወኢይፍታሕ ፡ በዘሰከየ ፡ እስከ ፡ ያዜክር ፡ ንዋየ ፡ ዘእሙር ፡ ከዋኔሁ ፡ ለንባብ ፡ ዘኢይትዌለጥ ፡ ከመ ፡ ዘይብል ፡ አነ ፡ ወሀብክዎ ፡ ፱ ፡ ዲናራተ ፡ ዘምስር ፡ ወበእንተ ፡ ዘኮነ ፡ ዲናራት ፡ ዘምስር ፡ ከዋኔሁ ፡ ውእቱ ፡ ዝንቱ ፡ ወበእንተ ፡ ዘኮነት ፡ ኍላቌሃ ፡ ፱ ፡ ውእቱ ፡ ወለእመኒ ፡ ሰከየ ፡ ሰከየተ ፡ ዘጥዩቅ ፡ ወዘይትሌቦ ፡ ይበሎ ፡ ለካልኡ ፡ ምንተ ፡ ትብል ፡ ወለእመኒ ፡ አምነ ፡ ወእምዝ ፡ ይበሎ ፡ ለሰካዪ ፡ ናሁ ፡ ተአመነ ፡ ለከ ፡ ወለእመ ፡ ኅሠሠ ፡ ንዋዮ ፡ ይፍታሕ ፡ ሎቱ ፡ በእንቲአሁ ፡ ላዕለ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ። ወእመኒ ፡ ክሕዶ ፡ ለዘሰከየ ፡ ኪያሁ ፡ ይበሎ ፡ ለዘክሕደ ፡ ብከኑ ፡ ሰምዕ ፡ ወለእመ ፡ ይቤ ፡ አልቦ ፡ ይበሎ ፡ ለካዪ ፡ ትምሕሎኑ ፡ ወእመኒ ፡ ፈርሀ ፡ መሐላ ፡ ወአግብአ ፡ ለዘሰከየ ፡ ወእመኒ ፡ መሐለ ፡ ዘሰከየ ፡ ደለዎ ፡ ነሢአ ፡ ንዋዮ ። ወእመሰ ፡ ይቤ ፡ ካልኡ ፡ እምድኅረ ፡ ፈርሀ ፡ መሐላ ፡ አነ ፡ እምሕል ፡ ኢይሰምዖ ፡ እምኔሁ ፡ ዘእንበለ ፡ በሥምረተ ፡ ካልኡ ፡ አው ፡ ገብአ ፡ ውስተ ፡ ካልእ ፡ ዓውደ ፡ ምኩናን ፡ ወኢአበየ ፡ ተመይጦ ፡ እመሐላ ፡ ኢይትከላእ ።

፩ሺ.፬፻፸፪ ወዘኒ ፡ ይቤ ፡ ብየ ፡ ጥያቄ ፡ ሰማዕት ፡ ከሡተ ፡ ወኅሠሠ ፡ መሐላ ፡ ዕድው ፡ እምበዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ እምቅድመ ፡ ያብጽሕ ፡ ኪያሁ ፡ ኢየምሕሎ ፡ ሎቱ ፡ ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ሰካዪ ፡ ብየ ፡ ጥያቄ ፡ ሰማዕት ፡ ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ እምድኅረ ፡ አበየ ፡ ይሰምዕዎ ። ወለእመ ፡ ኮኑ ፡ ሰማዕታቲሁ ፡ ኢአከልያነ ፡ ይትኀሠሥዎ ፡ ከመ ፡ ይወስክ ፡ ለአጠይቆ ። ወለእመ ፡ ኮኑ ፡ ራትዓነ ፡ ወፍርሃት ፡ ውስቴቶሙ ፡ ይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይፍልጥ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ወይሕትቶሙ ፡ ለለ፩ዱ ፡ ለኵሉ ፡ በእንተ ፡ ከዊነ ፡ ስምዕ ፡ ወጥያቄሁ ፡ ወመከና ፡ በከመ ፡ ገብረ ፡ ዳንኤል ፡ በጊዜ ፡ ረበናት ፡ እለ ፡ ኮኑ ፡ ሰምዐ ፡ ላዕለ ፡ ሶስና ። ወለእመ ፡ ገብሩ ፡ ይትጌሠጽዎ ፡ በባሕቲቶሙ ፡ በአፍርሆ ፡ ወበተግሣጽ ፡ እምግብራት ፡ ኃላፍያት ፡ ወኢኃላፍያት ፡ ወሰለተ ፡ ዕድሜ ፡ ወአዘክሮ ፡ በዘኮነ ፡ ቀዲሙ ፡ እምተግሣጽ ፡ እምላካዊ ፡ ላዕለ ፡ እለ ፡ ኮኑ ፡ ሰምዐ ፡ በሐሰት ፡ ወእምነ ፡ እማርያት ፡ መንፈሳውያት ፡ እስመ ፡ ገቢአ ፡ ኀበ ፡ ርትዕ ፡ ይኄ

ስለ ፡ ዳኞ ።

ወይም ፡ ክፉ ፡ ቃል ፡ ቢናገር ፡ ይከልክለው ። ቢደግምም ፡ ይቅጣው ። ቢጨምርም ፡ ይለየው ።

፩ሺ.፬፻፸፩ በማይታወቅ ፡ ሥራ ፡ የከሰሰውንም ፡ ስለእርሱ ፡ የከሰሰበትን ፡ ነገር ፡ አስረዳ ፡ ይበለው ። የታወቀ ፡ የገንዘቡን ፡ አኳኋን ፡ በማይለወጥ ፡ አነጋገር ፡ እስኪያስረዳ ፡ ድረስ ፡ በከሳሹ ፡ አይፍረድበት ። እኔ ፡ አምሳ ፡ የምስር ፡ዲናር ፡ ሰጠሁት ፡ እንደሚል ፡ ነው ። የምስር ፡ ዲናር ፡ ሁኔታዋ ፡ ይህ ፡ ስለሆነ ፡ ቍጥሯም ፡ ፶ ፡ ስለሆነ ፡ ነው ። የታወቀ ፡ የተረዳ ፡ ክስ ፡ ቢከስ ፡ ግን ፡ ተከሳሹን ፡ ምን ፡ ትላለህ ? ይበለው ። ቢያምን ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከሳሹን ፡ እነሆ ፡ አምኖልሃል ፡ ይበለው ። ገንዘቡን ፡ ቢፈልግ ፡ ስለርሱ ፡ በባለ ፡ ዕዳው ፡ ላይ ፡ ይፍረድለት ። የከሰሰውን ፡ ቢክደው ፡ የካደውን ፡ ምስክር ፡ አለህን ? ይበለው ። የለኝም ፡ ቢል ፡ ከሳሹ ፡ ትምላለህን ? ይበለው ። መሐላውን ፡ ፈርቶ ፡ ለከሳሹ ፡ ቢመልስ ፡ (አንተ ፡ ማል ፡ ቢለው) ፡ ከሳሹም ፡ ቢምል ፡ ገንዘቡን ፡ መቀበል ፡ ተገባው ። ተከሳሽ ፡ መሐላውን ፡ ከፈራ ፡ በኋላ ፡ እኔ ፡ እምላለሁ ፡ ቢል ፡ በከሳሽ ፡ ፈቃድ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አይስሙት ። ወይም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ የፍርድ ፡ ሸንጎ ፡ ቢመለስ ፡ (ይግባኝ ፡ ቢል) ፡ ከመሐላም ፡ መመለስን ፡ እንቢ ፡ ባይል ፡ አይከልከል ።

፩ሺ.፬፻፸፪ የታወቀ ፡ የምስክር ፡ ማስረጃ ፡ አለኝ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ባላጋራው ፡ ከባለዕዳው ፡ መሐላን ፡ ቢፈልግ ፡ እርሱን ፡ ሳያቀርብ ፡ አያምሉለት ። ከሳሽ ፡ የምስክር ፡ ማስረጃ ፡ አለኝ ፡ ቢል ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ እንቢ ፡ ካለ ፡ በኋላ ፡ አለብኝ ፡ ቢል ፡ ይስሙት ። ምስክሮቹ ፡ የማይበቁ ፡ ቢሆኑ ፡ ለማረጋገጥ ፡ እንዲጨምር ፡ ይጠይቁት ። ቅኖች ፡ ቢሆኑ ፡ ፍርሃትም ፡ ቢኖራቸው ፡ በመካከላቸው ፡ለይቶ ፡ እያንዳንዳቸውን ፡ ስለሚመሰክሩበት ፡ ሁኔታ ፡ ስለማስረጃውና ፡ ስለቦታዋ ፡ ሊመረምራቸው ፡ ይገባዋል ። ዳንኤል ፡ በሶስና ፡ ላይ ፡ ምስክር ፡ በሆኑ ፡ በሁለቱ ፡ ረበናት ፡ እንዳደረገ ። ቢተባበሩ ፡ ካለፉትና ፡ካላለፉት ፡ ሥራዎች ፡ ከሰለተ ፡ ምትም ፡ የተነሣ ፡ በማስፈራራትና ፡ በማስገረም ፡ ከዚህ ፡ አስቀድሞ ፡ በሐሰት ፡ ምስክር ፡ በሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ከአምላካዊ ፡ ቅጣትና ፡ ከመንፈሳውያት ፡ ምልክቶች ፡ የተነሣ ፡ በማሳሰብ ፡ ይቅጣቸው ። ከንቱ ፡ ነገርን ፡ በመሥራት ፡ ከመደፋፈር ፡ ወደቅንነት ፡

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ይስ ፡ እምትኃጥእ ፡ ላዕለ ፡ ገቢረ ፡ ከንቱ ፡ እስመ ፡ እምገቢረ ፡ ከንቱ ፡ ንስሐ ፡ እምእሁ ። ወአዝልፎሰ ፡ ላዕለ ፡ ገቢረ ፡ ከንቱ ፡ ወስከ ፡ ኃጢአት ፡ በዲበ ፡ ኃጢአት ።

፩ሺ.፬፻፸፫ ወእመ ፡ ጸንዐ ፡ እምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ ላዕለ ፡ ስምዐ ፡ ከዊን ፡ ወፍርሀት ፡ ሀሎ ፡ ውስቴቶሙ ፡ ይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይበሎ ፡ ለዘሰከዮ ፡ ንዋ ፡ ኮኑ ፡ ስምዐ ፡ ላዕሌከ ፡ እገሌ ፡ ወእገሌ ፡ ወተወከፍከ ፡ ስምዖሙ ፡ ወንዋ ፡ አባሕኩከ ፡ እምተናቅፎ ፡ ሰማዕት ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ በአጠይቆ ፡ ሰማዕት ። ወሰእመ ፡ ተንፍቀ ፡ ሰማዕታት ፡ በጥያቄ ፡ እመኒ ፡ ኮሎሙ ፡ እው ፡ ተርፈ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ትትዌጥል ፡ ሰማዕት ፡ ቀዳሚት ፡ እንተ ፡ አምጽአት ፡ ዕዳ ፡ በዘሰከዮ ፡ ቦቱ ፡ ወናሁ ፡ ተፈልጠ ፡ ፩ዱ ፡ እምአለ ፡ ይከውኑ ፡ ስምዐ ።

፩ሺ.፬፻፸፬ ክፍል ፡ ፪ቱ ፡ ወእመኒ ፡ አርመመ ፡ ዘሰከዮ ፡ ወኢአምነ ፡ ወኢክሕደ ፡ ይበሎ ፡ ፈታሒ ፡ ዳግመ ፡ በኑኃሁ ፡ ተሠጥዎ ፡ አውሥእ ፡ ወእመ ፡ አከሰ ፡ ይደልወከ ፡ ቃለ ፡ መሐላ ፡ አው ፡ ተሐባዩ ፡ ሀብ ፡ በዘሰከዩከ ። ወሰእመ ፡ ይቤ ፡ ዘሰከዮ ፡ ብየ ፡ ሰማዕት ፡ ከመ ፡ አልቦቱ ፡ ምንትኒ ፡ እምኀቤየ ፡ በዘይሰከየኒ ፡ የሀብዎ ፡ መዋዕለ ፡ ዕድሜ ፡ ለአብጽሖቶ ፡ ጥያቄሁ ፡ ወሰከዩኒ ፡ ይኑድግ ፡ እስከ ፡ ያመጽእ ፡ ሰማዕተ ። ወለእመ ፡ ተድኅረ ፡ እምነ ፡ ዕድሜ ፡ ዘየደሎ ፡ ለአብጽሖተ ፡ ጥያቄሁ ፡ ይደልዎ ፡ እመሂ ፡ መሐላ ፡ አው ፡ አሚን ። ወለእመኒ ፡ ኮነ ፡ ብዙኀ ፡ ንገር ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ለሰማዕት ፡ ይፍትሑ ፡ ለዘሞዐ ፡ እምኔሆሙ ። ወለእመ ፡ ኢነሥአ ፡ ቃለ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይፍትሑ ፡ በሀልዎቶሙ ፡ ከመ ፡ ይፈትሑ ፡ በኢሀልዎቶሙ ። ወቃልኒ ፡ ቃሉ ፡ ለዘሀሎ ፡ ንዋዩ ፡ ውስተ ፡ እዴሁ ፡ ምስለ ፡ መሐላሁ ፡ ለእመ ፡ ኢያምጽአ ፡ ሰማዕተ ፡ ላዕለ ፡ ካልኡ ፡ በእንተ ፡ ወሊዶቱ ።

፩ሺ.፬፻፸፭ ወዘእሰተዋደየ ፡ ወዘተበየወ ፡ ላዕለ ፡ ብእሲት ፡ እንተ ፡ ኢለመደት ፡ ተፋትሖ ፡ ወኢሐዋረ ፡ ፍኖት ፡ ኀበ ፡ ተማይጦ ፡ ወተናግሮ ፡ ኢየገብርዋ ፡ ለበጺሕ ፡ አላ ፡ ተአዝዝ ፡ ከመ ፡ ትሚም ፡ ላቲ ፡ ዘየንቲሃ ፡ ዘይተሠውም ፡ በምትክማ ። ወእምከመ ፡ ይለወ ፡ ላዕሌሃ ፡ መሐላ ፡ ይፈኑ ፡ ኀቤሃ ፡ ዘያምሕላ ፡ ፩ደ ፡ እምፈትሕን ።

፩ሺ.፬፻፸፮ ወይደልዎ ፡ ለፈታሒ ፡ ከመ ፡ ይጽሐፍ ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

መመለስ ፡ ይሻላልና ። ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ከመሥራት ፡ መመለስ ፡ ንስሐ ፡ ነውና ። ከንቱ ፡ ነገርን ፡ በመሥራት ፡ ማዘውተር ፡ ግን ፡ በኃጢአት ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ መጨመር ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፸፫ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ምስክር ፡ በመሆን ፡ ቢጸኑ ፡ ፍርሃትም ፡ ቢኖራቸው ፡ የከሰሱትን ፡ ሰው ፡ እገሌና ፡ እገሌ ፡ እነሆ ፡ ምስክር ፡ ሆነውብሃል ። ምስክርነታቸውንም ፡ ተቀብለሃል ። ምስክርነታቸውንም ፡ ለመንቀፍ ፡ ፈቅጄልሀ ፡ ነበር ፡ ብሎ ፡ በምስክሮች ፡ አስረጅነት ፡ በመካከላቸው ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። ምስክሮችም ፡ በማስረዳት ፡ ጊዜ ፡ ቢለያዩ ፡ ሁሉም ፡ ወይም ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ ቢቀር ፡ በተከሳሹ ፡ ላይ ፡ ዕዳ ፡ ያመጣችበት ፡ የቀደመችቱ ፡ ምስክርነት ፡ ትፈርሳለች ። ምስክር ፡ ከሆኑት ፡ ሰዎች ፡ አንዱ ፡ እነሆ ፡ ተለይቷልና ።

፩ሺ.፬፻፸፬ ክፍል ፡ ፪ ። የተከሰሰው ፡ ዝም ፡ ቢል ፡ ባያምን ፡ ወይም ፡ ባይክድ ፡ ዳግመኛም ፡ ዳኛው ፡ መልስ ፡ በመሻት ፡ መልስ ፡ ስጥ ፡ ያም ፡ ባይሆን ፡ የመሐላ ፡ ቃል ፡ ይገባሃል ፡ ወይም ፡ በከሰሱህ ፡ ነገር ፡ ዋስ ፡ ስጥ ፡ ይበለው ። የከሰሱት ፡ ሰው ፡ በከሰሰኝ ፡ ነገር ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ምንም ፡ እንደሌለው ፡ ምስክር ፡ አለኝ ፡ ቢል ፡ መረጃውን ፡ ለማቅረብ ፡ የቀጠሮ ፡ ቀን ፡ ይስጡት ። ከሳሹም ፡ ምስክሮቹን ፡ እስኪያመጣ ፡ ይተወው ። መረጃውን ፡ ለማቅረብ ፡ ከሚገባው ፡ ቀጠሮ ፡ ወደኋላ ፡ ቢል ፡ መሐላ ፡ ወይም ፡ ማመን ፡ ቢሆን ፡ ይገባዋል ። በምስክሮች ፡ መካከል ፡ የነገር ፡ ብዛት ፡ ቢሆን ፡ ከእነርሱ ፡ ላቸነፈው ፡ (ለበዛው) ፡ ይፍረዱ ። ከእነርሱ ፡ ያንዱ ፡ ቃል ፡ ባይበልጥ ፡ ባለመኖራቸው ፡ እንደሚፈርዱ ፡ በመኖራቸው ፡ ይፍረዱ ። ስለ ፡ መካዱም ፡ በተከሳሹ ፡ ላይ ፡ ምስክር ፡ ካላመጣ ፡ ነገሩ ፡ ከመሐላው ፡ ጋራ ፡ በእጁ ፡ ገንዘብ ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ ነገር ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፸፭ መፋረድን ፡ ወደገበያ ፡ መንገድ ፡ መሄድን ፡ መንገድን ፡ ያለመደችውን ፡ ሴት ፡ ደፍሮ ፡ የከሰሰ ፡ ሰው ፡ ከዳኛ ፡ ድረሽ ፡ ብለው ፡ አያስገድዷት ። በመቋሚያዋ ፡ የሚተካ ፡ ነገረ ፡ ፈጅ ፡ ትሾም ፡ ዘንድ ፡ ትዘዝ ፡ እንጂ ፡ ለእርሷ ፡ መሐላ ፡ ከተገባትም ፡ የሚያምላት ፡ ከዳኞች ፡ ወገን ፡ አንዱን ፡ ወደ ፡ እርሷ ፡ ይላክ ።

፩ሺ.፬፻፸፮ ለዳኛ ፡ በ፪ ፡ ወይም ፡ በሚበዛ ፡ ምስክር ፡

ለተፋትሖ ፡ መጽሐፈ ፡ ዕውቀ ፡ ወፍሉጠ ፡ ኅበ ፡ ካልእ ፡ ፈታሒ ፡ እንዘ ፡ ይከውን ፡ በውስቴቱ ፡ ስምዐ ፡ ላዕለ ፡ ነፍሱ ፡ በስምዐ ፡ ፪ቱ ፡ እው ፡ ዘይፈያፍድ ፡ ወስውእቱ ፡ ፈታሒ ፡ ካልእ ፡ ያይ ልዎ ፡ ከመ ፡ ይነጽር ፡ ውስተ ፡ ጠይቆተ ፡ ፍትሑ ፡ ወእምዝ ፡ ይፍታሕ ፡ ቦቱ ፡ ሰበ ፡ ተወከፈ ፡ ስምዖሙ ፡ ለሰማዕታት ፡ ዘውስቴቱ ። ወፍጻሜ ፡ ምዕራፍ ፡ ሳብዕ ፡ በእንተ ፡ ፍትሐት ፡ ናሁ ፡ ይነግር ፡ በበእንቀጸ ፡ ፍትሑ ፡ ዘከመ ፡ ጕልታት ፡ ወከዊነ ፡ ግዕዛን ፡ ወአንብሮ ፡ ማኅ ፀንት ፡ ወትውህበታት ፡ ወሤጥ ፡ ወተዓስቦ ፡ ወተዋርሶ ፡ ወጽሒፈ ፡ ትእዛዝ ፡ ወዘይመስሉ ፡ ለዝንቱ ።

ራሱ ፡ በውስጡ ፡ ምስክር ፡ ሁኖ ፡ ስመፈራረድ፡ የታወቀና ፡ የተለየ ፡ መዝገብ ፡ ወደሌላ ፡ ዳኛ ፡ ሊጽፍ ፡ ይገባዋል ። ለዚያም ፡ ስሌላው ፡ ዳኛ ፡ የፍርዱን ፡ እርግጠኛነት ፡ ሊመለከት ፡ ይገባ ዋል ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ በውስጡ ፡ ያሉትን ፡ የምስ ክሮችን ፡ ምስክርነት ፡ በተቀበለ ፡ ጊዜ ፡ (ከተቀ በለ ፡ በኋላ) ፡ ይፍረድበት ። የሰባተኛው ፡ ምዕራፍ ፡ መጨረሻ ፡ ስለፍርዶች ፡ እነሆ ፡ በየፍ ርዱ ፡ እንቀጽ ፡ ይናገራል ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ ጉልቶች ፡ እንደ ፡ ነጻነት ፡ ሁኔታ ፡ እንደ ፡ አደራ ማስቀመጥ ፡ እንደ ፡ ትውስቶችና ፡ እንደዋጋ ፡ እንደኪራይና ፡ እንደውርስ ፡ ትእዛዝን ፡ እንደ መጻፍና ፡ ይህንም ፡ እንደሚመስለው ፡ ያለ ፡ ነው ።

፩ሺ፱፻፹፯ ምዕራፍ ፡ ሳምን ፡ በእንተ ፡ ገቢረ ፡ ዕርቅ ። ገቢረ ፡ ዕርቅሰ ፡ እዙዝ ፡ ውእቱ ፡ በእንተ ፡ ዘይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ "ሑር ፡ ቅድመ ፡ ወተዐረቅ ፡ ምስለ ፡ እኁከ ፡ ወእምዝ ፡ ገቢእከ ፡ አብእ ፡ መባእከ ። ወብፁዓንሰ ፡ ከዕበ ፡ ብፁ ዓን ፡ ገብርያነ ፡ ሰላም ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ውሉ ደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰመዩ ። ወሐዋርያትኒ ፡ ይቤሉ ፡ ኢመፍትው ፡ ለእግብርተ ፡ ክርስ ቶስ ፡ ተጻልአ ።

፩ሺ፱፻፹፯ ስምንተኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ዕርቅ ፡ ስለማድረግ ፡ ይናገራል ። ዕርቅ ፡ ማድረግስ ፡ የታዘዘ ፡ ነው ። ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ አስቀድመህ ፡ ሂድና ፡ ከወንድምህ ፡ ጋር ፡ ታረቅ ። ከዚያም ፡ ተመል ሰህ ፡ መባህን ፡ ስጥ ፡ ስላለ ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፳፫ - ፳፬) ። ዳግመኛም ፡ ዕርቅን ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ እነርሱ ፡ የእግዚአብ ሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉና ፡ በማለቱ ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፱) ። ሐዋርያትም ፡ ለክርስቶስ ፡ አገ ልጋዮች ፡ መጣላት ፡ አይገባቸውም ፡ ብለዋል ።

፩ሺ፱፻፹፰ ዘኤፌሶን ፡ ፫ቱ ፡ ወይኩን ፡ ዘይፀውሮ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔከሙ ፡ ለካልኡ ፡ ወኩኑ ፡ ዕቁባነ ፡ በዐ ቂበ ፡ ፍቅር ፡ መንፈሳዊት ፡ በማእሰረ ፡ ዕርቅ ። ዘ፬ቱ ፡ ወኢታዕርቡ ፡ ዐሐየ ፡ ዲበ ፡ መዓትክሙ፡ ወኢታህብዎ ፡ ፍኖተ ፡ ለሰይጣን ፡ ለእስሕቶት ክሙ ።

፩ሺ፱፻፹፰ ኤፌሶን ፡ ፫ ። ከእናንተ ፡ አንዱ ፡ ሌላውን ፡ የሚሸከመው ፡ ይሁን ። በዕርቅ ፡ ማሠሪያነት ፡ መንፈሳዊት ፡ ፍቅርን ፡ በመጠበቅ ፡ የተጠበቃ ችሁ ፡ ሁኑ ። (ኤፌ ፡ ፬ ፡ ፩ - ፫) ። ፬ ። በቁጣችሁ ላይ ፡ ፀሐይን ፡ አታስገቡ ። ለይጣንም ፡ እንዲያ ስታችሁ ፡ ጐዳና ፡ አትስጡት ። (ኤፌ ፡ ፬ ፡ ፳፮ - ፳፯) ።

፩ሺ፱፻፹፱ ድስቅ ፡ ፳ቱ ፡ ወተዐቀቡ ፡ ከመ ፡ ትግበሩ ፡ ሰላመ ፡ ማእከለ ፡ ተጻላእያን ፡ እምቅድመ ፡ ይፃእ ፡ ፍትሕ ፡ እምኤጲስቆጶስ ፡ ወተፋትሖሰ ፡ ኢኮነ ፡ ሠናየ ፡ በምንትኒ ፡ ግሙራ ፡ እመፍቅ ዳተ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ እስመ ፡ እመንድቦተ ፡ ፩ዱ ፡ ለካልኡ ፡ በምንትኒ ፡ እመፍቅዳተ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ እምግብረ ፡ ሰይጣን ፡ ውእቱ ፡ ወእመከራሁ ። ወያፍቅሮን ፡ ሰብእ ፡ ወይሥዐር ፡ ዘንተ ፡ በጕጕዓ ፡ ወለእመኒ ፡ ውእቱ ፡ የኀጕል፡ ኅዳጠ ፡ እምንዋይ ፡ ይኄይሰከ ፡ ከመ ፡ ትኅ ጕል ፡ ኅዳጠ ፡ እምንዋይከ ፡ ወትኅጕእ ፡ ለተ

፩ሺ፱፻፹፱ ድስቅ ፡ ፳ ። ከኤጲስቆጶስ ፡ ፍርድ ፡ ሳይወጣ፡ በተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ ዕርቅ ፡ ከማድረግ፡ ተጠበቁ ። ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ፈቃድ ፡ የተነሣ ፡ በማ ንኛውም ፡ ነገር ፡ መካሰስ ፡ ክቶ ፡ መልካም ፡ አይደለም ። ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ፈቃድ ፡ የተነሣ ፡ በማንኛውም ፡ ነገር ፡ አንዱ ፡ ሌላውን ፡ ማስጨ ነቅ ፡ ከሰይጣን ፡ ሥራ ፡ ከፈተናው ፡ የተገኘ ፡ ነውና ። ሰው ፡ ፈጥኖ ፡ በችኮላ ፡ ይህን ፡ ይሻር ። እርሱ ፡ ከገንዘቡ ፡ ጥቂት ፡ ቢያጠፋ ፡ አንተም ፡ ከገንዘብህ ፡ ጥቂት ፡ ብታጠፋ ፡ ከሰውም ፡ ሁሉ፡ ጋር ፡ ወንድሜ ፡ ወንድሜ ፡ ለመባባል ፡ ብትቸ

አንቀጽ ፡ ፹፫ ።

አንዎተ ፡ ዙሉ ፡ ሰብእ ፡ እኮ ፡ ለአኃዊከ ፡ ባሕቲቶሙ ፡ እላ ፡ ምስለ ፡ ዙሎሙ ፡ እሕዛብ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ ለእመ ፡ ኀጕልከ ፡ ዘዝንቱ ፡ ዓለም ፡ እኮ ፡ ዘተኀጕል ፡ እም ፡ ዘእግዚአብሔር እምከመ ፡ ኮንከ ፡ ሳእከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘተሐዩ ፡ በትእዛዘ ፡ ክርስቶስ ። ለእለ ፡ ተበእሱ ፡ እስተጋብእዎሙ ፡ በተፋቅሮ ፡ ወለመስተጻርራን ፡ እስተሳልምዎሙ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ሰንእዋን ፡ እስመ ፡ እግዚእን ፡ ይቤ ፡ ብፁዓን ፡ ገባርያን ፡ ሰላም ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ውሉደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያሰምዩ ።

፩ሺ፬፻፹ ዘ፲ወ፪ቱ ፡ ወእለሰ ፡ ይገብሩ ፡ ጽልአ ፡ ወጸብአ ፡ ወተጋእዞ ፡ ወተፋትሖ ፡ ዐማፅያን ፡ እሙንቱ ፡ ወነኪራን ፡ እምእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላከ ፡ ምሕረት ፡ ውእቱ ።

፩ሺ፬፻፹፩ ዘቆሮንቶስ ፡ ፮ቱ ፡ "ናሁ ፡ እኩንንከሙ ፡ ሥጋከሙ ፡ ቅድመ ፡ እመ ፡ ኮንከሙ ፡ ተጻላእያን ፡ ወትትገአዙ ፡ በበይናቲከሙ ፡ ወለምንት ፡ ዘኢትትዔገሉ ፡ ወለምንት ፡ ዘኢትትገፍዑ ፡ እላ ፡ እንትሙሰ ፡ ተዓጋልያን ፡ ወገፋዕያን ፡ እኃዊከሙ ፡ ካዕበ ፡ ኢተአምሩኑ ፡ ከመ ፡ ዐማፅያን ፡ ኢይወርስዋ ፡ ለመንግሥተ ፡ እግዚአብሔር" ።

፩ሺ፬፻፹፪ ወእእምር ፡ ከመ ፡ ዕርቅ ፡ ዘበእንተ ፡ ንዋይ ፡ በፍኖተ ፡ እርዮት ፡ ወውሂቦት ፡ ሰቢዝዎ ፡ መሐላ ፡ ወመተረ ፡ ተጻልኦ ፡ ወተፋትሖ ፡ በእንተ ፡ ፈቃደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወኀፊር ፡ እምሰብእ ። ወውእቱ ፡ ይትከፈል ፡ ኀበ ፡ ፫ቱ ፡ እክፋል ፡ ተዓርቆ ፡ ዘምስለ ፡ ተእምኖ ፡ ወዕርቅ ፡ ዘምስለ ፡ ክሒድ ፡ ወዕርቅ ፡ ዘምስለ ፡ እርምሞ ፡ ወውእቱ ፡ ሶበ ፡ ኢየአምን ፡ በዘይስእልዎ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወኢይክሕዶ ።

፩ሺ፬፻፹፫ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዕርቅ ፡ በእንተ ፡ ንዋይ ፡ በውሂበ ፡ ንዋይ ፡ ይትፈጸም ፡ በእንቲአሁ ፡ ውሂበ ፡ ንዋይ ፡ በእንተ ፡ ንዋይ ። ወይኩን ፡ ዘከመ ፡ ይትገበሩ ፡ በምሥያጥ ፡ ወተማይጦ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዕርቅ ፡ በእንተ ፡ ንዋይ ፡ ዘበቱ ፡ በቀኑዓት ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ተዐሰበ ፡ ወኵሉ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ውስቴቱ ፡ ርዴ ፡ በአምሳል ፡ ለእመ ፡ ይከውን ፡ ዕርቅ ፡ በእንተ ፡ ፳ ፡ ርኩብት ፡ በጊዜሃ ፡ ወ፲ ፡ በዕድሜ ፡ እው ፡ በመስፈርት ፡ እው ፡ በእንተ ፡ ሥርናይ ፡ ብሉይ ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

ኩል ፡ ይሻልሃል ። ለወንድሞችህ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ። ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡ እንጂ ። በክርስቶስ ፡ ትእዛዝ ፡ የምትኖር ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገልጋይ ፡ ከሆንክ ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ገንዘብ ፡ ብታጣ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የሚገኘውን ፡ የምታጣ ፡ አይደለህምና ። የተጣሉትን ፡ ሰዎች ፡ በፍቅር ፡ አንድ ፡ አድርጋቸው ። የተጣሉትንም ፡ አስታርቃቸው ። የተስማሙ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ። ጌታችን ፡ ሰላምን ፡ የሚያደርጉ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። እነርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉና ፡ ብሏልና ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፱) ።

፩ሺ፬፻፹ ፲፪ ። ጠብን ፡ መጣላትን ፡ ክርክርንና ፡ መፋረድን ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ዓመፀኞች ፡ ናቸው ። ከእግዚአብሔርም ፡ የተለዩ ፡ ናቸው ። እግዚአብሔር ፡ የይቅርታ ፡ አምላክ ፡ ነውና ።

፩ሺ፬፻፹፩ ቆሮንቶስ ፡ ፮ ። እነሆ ፡ እርስበርሳችሁ ፡ የምትጣሉና ፡ የምትከራከሩ ፡ በነበራችሁበት ፡ ጊዜ ፡ ሥጋችሁን ፡ አስገዝታችሁ ፡ ነበረ ። የማትቀሙ ፡ ለምንድን ፡ ነው ? የማትበደሉስ ፡ ለምንድን ፡ ነው ? እናንተስ ፡ ገና ፡ ሁለተኛ ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ የምትቀሙ ፡ የምትበድሉም ፡ ናችሁ ። ዓመፀኞች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ እንዳይወርሱ ፡ አታውቁምን ? (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፯ - ፲፩) ።

፩ሺ፬፻፹፪ ስለታወቀ ፡ ገንዘብ ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ በማስተካከል ፡ መንገድ ፡ መሐላን ፡ ለመበዝበዝ ፡ (ለማስቀረት) ፡ ስለእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ከሰው ፡ ስለማፈር ፡ መፋረድንና ፡ መጣላትን ፡ ለመቁረጥ ፡ እንደሆነ ፡ እወቅ ። እርሱም ፡ ከ፫ ፡ ይከፈላል ። ከማመንም ፡ ጋራ ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ ከመካድም ፡ ጋር ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ ከዝምታም ፡ ጋር ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ አለ ። ይኸውም ፡ በከሰሱት ፡ ነገር ፡ ባያምን ፡ ወይም ፡ ባይክድ ፡ ነው ።

፩ሺ፬፻፹፫ ስለገንዘብ ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ ገንዘብ ፡ በመስጠት ፡ ቢሆን ፡ ስለእርሱ ፡ የገንዘብ ፡ ስጦታ ፡ ስለገንዘብ ፡ ይፈጸማል ። በመሸጥና ፡ በመግዛት ፡ ጊዜ ፡ እንደሚያደርጉት ፡ ይሁን ። ዕርቁ ፡ ትርፍ ፡ ስላለው ፡ ገንዘብ ፡ ቢሆን ፡ እንደተዋዋሉት ፡ ይሁን ። አራጣ ፡ ከሌለበት ፡ ሁሉ ፡ የተገባ ፡ ነው ። ለምሳሌ ፡ ዕርቁ ፡ በጊዜዋ ፡ በተገኙ ፡ በኪያ ፡ በቀጠሮ ፡ ፲ ፡ ወይም ፡ በመስፈሪያ ፡ ወይም ፡ ስለከረመ ፡ ስንዴና ፡ አዲስ ፡ ስንዴ ፡ በቀጠሮ ፡ ስለመስጠት ፡ ቢሆን ፡ በእ

እንቀጽ : ፵፰ ።

ዘተቀብ : ጥቀ ። ወለእመ : ተመይጠ : ደኀረ : ንስሓሁ : ወገብረ : በአምሳለ : ዝንቱ : ይፃእ : እምክህነቱ : ባሕቱ : ኢይክልእዎ : እምተሳትፎ : ምእመናን : ወቍርባን ። ወለእመ : ኮነ : ዘአውሰበ : ወብእሲቱ : ምስሌሁ : ውስተ : ቤቱ : ይግበሩ : ቦቱ : በአምሳለ : ዝንቱ : ክሰበት : ዘከመ : ቀዳሚ : ንስሓ ።

፩ሺ፯፻፵፫ ወዲያቆንኒ : ይኩን : በቀዳሚ : በአምሳለ : ቀሲስ : ወለእመ : ተመይጠ : በዳግም : ንስሓሁ : ፩ዱ : ዓመት : ወእመ : ተመይጠ : በሣልስ : ይፃእ : እምክህነቱ : ለእመ : ኮነ : ዘአልቦቱ : ብእሲት : ወእመኒ : ሀለወት : ብእሲቱ : ውስተ : ቤቱ : ይትኀደግ : በንስሓ : ደኀረ : ተሰደ : ፫ተ : ዓመተ : ወበፍጻሜ : ፫ቱ : ዓመት : ይትመየጥ : ኀበ : ክህነቱ : ወእመሰ : ተመይጠ : እምድኅረዝ : ይፃእ : እምክህነቱ : ግሙራ ። ወፈድፋደሰ : ኤጲስቆጶስ : ይፃእ : ፍጹመ : እመ : ዓርገ : በአበሳሁ : ቀዳማዊ : ወአልቦቱ : ንስሓ : ዳእሙ : ኢይክልእዎ : እምተሳትፎተ : ምእመናን : ወንሢአ : ቍርባን ።

፩ሺ፯፻፵፬ ወቀሲስኒ : ዘአልቦቱ : ብእሲት : ይንስሕ : ወዘሰ : ቦቱ : ብእሲት : ኢይንስሕ ።

፩ሺ፯፻፵፭ ወዲያቆንኒ : ዘአልቦቱ : ብእሲት : ይንስሕ : ፪ተ : ጊዜያተ : ወዘቦቱ : ብእሲት : ፩ደ : ጊዜ : ወኢይክልእዎሙ : እምንሣእ : ቍርባን : ወተሳትፎተ : ምእመናን : አላ : ይክልእዎሙ : እምተልእኮ : ምሥዋዕ ።

፩ሺ፯፻፵፮ ወለእለ : ተርፉ : ክህናት : ወመነኮሳት : ወሕዝባውያን : ለእመ : አበሱ : በአምሳለ : ዝንቱ : አበሳ : ይፍትሑ : ላዕሌሆሙ : ሊቀ : ምኔት : ወራድእ : ዘከመ : ይደሉ : ለንስሓሆሙ : ባሕቱ : ኢያክብዱ : ቦሙ : ክበደ : ንስሓ : ጽኑዐ : ከመ : ኢይትኀጐሉ : ወኢይትኀደጉ : ክሰበ : ወኢይትዓሠርዎሙ : ከመ : ኢይማስኑ : ውስተ : ቀያእሙ : ወኀጢአቶሙ : ወኢይትመከዐቡ : ኀጐሎሙ : ወዘአበየ : ዘንተ : ትእዛዘ : ሲኖዶስ : ይትወገዝ ።

፩ሺ፯፻፵፯ ዳግም : በእንተ : እለ : ተርፉ : ምእመናን ። ኒቅያ : ዘ፸ወ፱ቱ : እመቦ : ብእሲ : ምእመን : ዘይተሉ : ብእሲተ : እንተ : ኢተአምን : አው : ብእሲት : ምእምንት : ዘትተሉ : ብእሲ : ዘኢየ

ስለ : ዝሙት : ቅጣት ።

ይሁን ። ከንስሐውም : በኋላ : ተመልሶ : ይህን፣ የመሰለ : ሥራ : ቢሠራ : ከክህነቱ : ይሻር ። ነገር : ግን : ከምእመናን : አንድነትና : ከቍርባን : አይከልክሉት ። ያገባ : ቢሆን : ሚስቱም፣ ከእርሱ : ጋር : ብትኖር : በዚህ : ምሳሌ : እንደ መጀመሪያው : ንስሓ : ሰጥና : ያድርጉበት ።

፩ሺ፯፻፵፫ ዲያቆንም : በመጀመሪያ : እንደ : ቄስ : ይሁን ። ቢመለስም : በሁለተኛው : ንስሐው : ፩ : ዓመት : ይሁን ። በ፫ኛ : ቢመለስ : ከክህነቱ : ይሻር ። ሚስት : የሌለችው : ከሆነ ። ሚስቱ : በቤቱ : ካለች : ፫ : ዓመት : ከተለየ : በኋላ : በንስሓ : ይቅርለት ። በ፫ : ዓመት : መጨረሻም : ወደ ክህነቱ : ይመለስ ። ከዚህ : በኋላ : ቢመለስ : ግን : ፈጽሞ : ከክህነቱ : ይሻር ። ይልቁንም : ኤጲስቆጶስ : በመጀመሪያ : ኃጢአቱ : ከሹመቱ : ፈጽሞ : ይሻር ። ከምእመናን : ጋር : ከመገናኘት : ቍርባን : ከመቀበል : አይከልክሉት : እንጂ : ንስሓ : የለውም ።

፩ሺ፯፻፵፬ ሚስት : የሌለችውም : ቄስ : በንስሐ : ይመለስ ። ሚስት : ያለችው : ግን : በንስሐ : አይመለስ ።

፩ሺ፯፻፵፭ ሚስት : የሌለችው : ዲያቆንም : ፪ት : ጊዜ : ሚስት : ያለችው : አንድ : ጊዜ : በንስሐ : ይመለስ ። ቍርባን : ከመቀበልና : ከምእመናን፣ አንድነት : አይከልክሏቸው ። ከመቅደስ : አገልግሎት : ይከልክሏቸው : እንጂ ።

፩ሺ፯፻፵፮ የቀሩት : ካህናትና : መነኮሳት : ሕዝባውያንም : ይህን : በመሰለ : በደል : ቢበድሉ : አበምኔቶና : ዳኛ : ለንስሓቸው : እንደሚገባ : ይፍረዱባቸው ። ነገር : ግን : እንዳይጎዱ : ዳግመኛም : እንዳይተዉ : ቀኖናውን : ፅኑ : አድርገው አያክብዱባቸው ። ወደቀደመ : ጥፋታቸውና : ኃጢአታቸው : እንዳይመለሱ : ቸል : አይበሏቸው ። ጥፋታቸውም : ሰፋ : ድርብ : እንዳይሆን : ይህን : ትእዛዝ : አልቀበልም : ያለውንም : ሲኖዶስ : ታወግዘዋለች ። (ትለየዋለች) ።

፩ሺ፯፻፵፯ ሁለተኛው : ስለቀሩት : ምእመናን : ይናገራል ። ኒቅያ : ፸፱ ። ያላመነችውን : ሴት : የሚከተል : አማኒ : ወንድ : ቢኖር : ወይም : አንዱ፣ ለአንዱ : ከሃይማኖት : ለመውጣት : ምክን

አንቀጽ ፡ ፵፰ ።

አምነ ፡ በምክንያተ ፡ ዝሙት ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ እሑዱ ፡ ለካልኡ ፡ ምክንያተ ፡ ወዲአ እምሃይማኖት ፡ ንስሐሆሙ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ተወፍዮ ፡ በአንቀጸ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ፲ተ ፡ ዓመተ ፡ በለቢስ ፡ ሠቅ ፡ ወንጺፈ ፡ ሐመድ ። ወእምድኅረ ፡ ዝ ፡ ይባኡ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በባሕቲቶሙ ፡ ተፈሊጦሙ ፡ ፭ተ ፡ ዓመተ ፡ ወኢይሳተፍዎሙ ፡ ስብአ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በአሚን ፡ ወቍርባን ። ወእምድኅረ ፡ ፍጻሜ ፡ ዓመት ፡ ይባርክ ፡ ቀሲስ ፡ ላዕለ ፡ ማይ ፡ ወዘይት ፡ በካልእ ፡ እምልማደ ፡ ተምቀት ፡ እንበለ ፡ ቅብዐ ፡ ሜሮን ፡ አላ ፡ ከመ ፡ ልማደ ፡ በረከት ፡ በላዕለ ፡ ማይ ፡ ወቅብዕ ፡ በእንተ ፡ ድዉያን ። ወእምዝ ፡ ይነሥእ ፡ ካህን ፡ እምውእቱ ፡ ማይ ፡ ወይነዝኅ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ወእሙንቱ ፡ እንዘ ፡ ይትአመኑ ፡ ወየኀድጉ ፡ ኃጢአቶሙ ፡ ወይትመይጡ ፡ ለሙ ፡ በጸሎት ። ወእምድኅረዝ ፡ የሀብዎሙ ፡ እምቍርባን ፡ ወዘተሰይመ ፡ ዘንተ ፡ ትእዛዘ ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዝ ።

፩ሺ፯፻፵፰ ረስጠጅ ፡ ፹ወ፮ቱ ፡ ረስጠብ ፡ ፵ወ፯ቱ ፡ እመሂ ፡ ሕዝባዊ ፡ ዘነሥአ ፡ ለድንግል ፡ ዘእኅፀዩ ፡ ሎቱ ፡ ወተንሥአ ፡ ላዕሌሃ ፡ ይትፈለጥ ፡ ወኢያውስብ ፡ ካልእተ ፡ በእንበሌሃ ፡ አላ ፡ ያውስብ ፡ ኪያሃ ፡ በከመ ፡ አፍቀራ ፡ እመኒ ፡ ኮነት ፡ ሕሥምተ ፡ አው ፡ ነዳይተ ።

፩ሺ፯፻፵፱ ዘዕንቀራ ፡ ፲ወ፱ቱ ፡ ወዘሂ ፡ ዘመወ ፡ ምስለ ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ምት ፡ ይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ከመ ፡ የእኅዝ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘውእቱ ፡ ፯ቱ ፡ ዓመት በከመ ፡ አቅደምነ ።

፩ሺ፯፻፶ ባስ ፡ ፲ወ፰ቱ ፡ ወዘቦቱ ፡ ብእሲት ፡ ሰእመ ፡ ዘመወ ፡ ይቱም ፡ ፯ተ ፡ ዓመተ ፡ በእፍኣ ። ወእመ ፡ ገብረ ፡ እምቅድመ ፡ ያውስብ ፡ ብእሲተ ፡ ንስሐሁ ፡ ፬ቱ ፡ ሱባዔ ፡ ወይገሥጽዎ ፡ ከመ ፡ ያውስብ ፡ ብእሲተ ፡ ወለእመ ፡ ኢፈተደ ፡ አውስቦ ፡ ይስድድ ፡ እስከ ፡ ያወስብ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ ይትገኃሥ ፡ እምዝሙት ።

፩ሺ፯፻፶፩ ዘ፲ወ፫ቱ ፡ ወዘሂ ፡ ዘመወት ፡ ብእሲቱ ፡ ለእመ ፡ ኢያእመረ ፡ ይደልዎ ፡ ኮኑኔ ፡ ንስሓ ፡ ለባሕቲታ ። ወእመ ፡ አእመረ ፡ ወኢፈተደ ፡ አውስኦታ ፡ ይባኡ ፡ ክልኤሆሙ ። ዘ፲ወ፬ቱ ፡ ወእመ ፡ ኮነ ፡ ካህነ ፡ ይደቅ ፡ እመንበሩ ፡ ወይትገኃሥ ፡ እምትመጥዎተ ፡ ምሥጢር ፡

ስለ ፡ ዝሙት ፡ ቅጣት ።

ያት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በዝሙት ፡ ምክንያት ፡ ያላመነ ፡ ወንድን ፡ የምትከተል ፡ አማኒት ፡ ሴት ፡ ብትኖር ፡ ንስሓቸው ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ማቅ ፡ በመልበስና ፡ አመድ ፡ በመነስነስ ፡ በአንቀጸ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መቆም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ብቻቸውን ፡ ተለይተው ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይግቡ ። የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሰዎችም ፡ አይ፟ ፡ በመነጋገርና ፡ በቍርባን ፡ አይገናኙዋቸው ። ዓመቱም ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ያለሜሮን ፡ ከጥምቀት ፡ ልማድ ፡ ልዩ ፡ በሆነ ፡ በውሃና ፡ በዘይት ፡ ላይ ፡ ቄስ ፡ ይባርክ ። ስለድውያን ፡ በውሃና ፡ በዘይት ፡ ላይ ፡ እንደሚያደርገው ፡ ያለ እንደ በረከት ፡ ልማድ ፡ ነው ፡ እንጂ ። ከዚህም በኋላ ፡ ቄሱ ፡ ከዚያ ፡ ውሀ ፡ እየታፈኑ ፡ ይረጩቸው ። እነርሱም ፡ ኃጢአታቸውን ፡ እያመኑ ይተዋሉ ። በጸሎትም ፡ ይሠረይላቸዋል ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከቍርባን ፡ ይስጧቸው ። ይህን ፡ ትእዛዝ ፡ ያፈረሰውንም ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዘዋል ። (ይለየዋል )።

፩ሺ፯፻፵፰ ረስጠጅ ፡ ፹፮ ። ረስጠብ ፡ ፵፯ ። ያላጩለትን ልጃገረድ ፡ የነጠቀ ፡ ሕዝባዊ ፡ ቢኖር ፡ ቢደፋፈራትም ፡ ይለይ ። ከእርሱዋም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ አያግባ ። መልክ ፡ ከፋም ፡ ብትሆን ፡ ደኃም ፡ ብትሆን ፡ እንደ ፡ ወደዳት ፡ እርሱዋን ፡ ያግባ ።

፩ሺ፯፻፵፱ ሰንቀራ ፡ ፲፱ ። ባል ፡ ካላት ፡ ሴት ፡ ጋራ ፡ ያመነዘረ ፡ ወንድ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ንስሓ ፡ ሊገባ ፡ ይገባዋል ። ይኸውም ፡ አስቀድመን ፡ እንደተናገርን ፡ ፯ ፡ ዓመት ፡ ነው ።

፩ሺ፯፻፶ ባስ ፡ ፲፰ ። ሚስት ፡ ያለችው ፡ ሰው ፡ ቢሰስን ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ በእፍኣ ፡ ይቁም ። ሚስት ፡ ከማግባቱ ፡ በፊት ፡ ቢያመነዝር ፡ ግን ፡ ንስሐው ፡ ፬ ፡ ሱባኤ ፡ ነው ። ሚስትም ፡ እንዲያገባ ፡ ይምከሩት ። ማግባትንም ፡ ባይወድ ፡ እስኪያገባ ፡ ድረስ ፡ ይለይ ። ያም ፡ ባይሆን ፡ ከዝሙት ፡ ይከልከል ።

፩ሺ፯፻፶፩ ፲፫ ። ሚስቱ ፡ የሰሰነችበት ፡ ሰው ፡ ቢያውቅ ፡ ለብቻዋ ፡ የንስሓ ፡ ቅጣት ፡ ይገባታል ። በውቆ ፡ ሊፈታት ፡ ባይወድ ፡ ግን ፡ ሁለቱም ፡ ይለዩ ። ፲፬ ። ካህን ፡ ቢሆን ፡ ከሹመቱ ፡ ይሻር ። ምሥጢርንም ፡ ከመቀበል ፡ ይራቅ ። (ይከልከል ። ተጸጽቶ ፡ ቢፈታት ፡ ግን ፡ ከምሥጢር ፡ ይስጡት ;

አንቀጽ ፡ ፵፰ ።

ወሶበ ፡ ነስሐ ፡ ወአውፅአ ፡ የዘብዎ ፡ እምሥጢር ፡ ባሕቲ ፡ ኢይትመየጥ ፡ ኅበ ፡ መዓርጉ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ተሳተፈ ፡ ዘማዊተ ።

፩ሺ፯፻፶፪ ሣልስ ፡ በእንተ ፡ ዘይዜሙ ፡ ምስለ ፡ አለ ሐሩም ፡ አውስቦቶን ። በስ ፡ ዘጽወሮቱ ፡ ወዘሂ ፡ ይዜሙ ፡ በወለተ ፡ ብእሲቱ ፡ ይፃእ ፡ ፲ወ፰ተ ፡ ዓመተ ፡ ፯ተ ፡ ዓመተ ፡ እንዘ ፡ ይበኪ ፡ ወ፩ተ ፡ ዓመተ ፡ እንዘ ፡ ይሰምዕ ፡ ቃለ ፡ ምዕዳን ፡ ወ፰ተ ፡ ዓመተ ፡ ቀዊሞ ፡ ምስለ ፡ ምእመናን ።

፩ሺ፯፻፶፫ ዘጽወ፬ቱ ፡ ወዘይዜሙ ፡ በእኅተ ፡ ብእሲቱ ፡ ይፃእ ፡ ፲ወ፩ተ ፡ ዓመተ ፡ ወከማሁ ፡ ብእሲትኒ ፡ እንተ ፡ ዘመወት ፡ በ፪ቱ ፡ አኃው ።

፩ሺ፯፻፶፬ ዘጽወ፭ቱ ፡ ወዘአውሰበ ፡ ፪ተ ፡ አኃተ ፡ ከማሁ ፡ ብእሲትኒ ፡ ዘትትወሰብ ፡ ለ፪ቱ ፡ አኃው ይትፈለጡ ፡ ወይኩኑ ፡ ታሕተ ፡ ሥርዓተ ፡ ንስሓ ፡ ወኢይሳተፍዎሙ ፡ እምባን ፡ በለወ ፡ በዝንቱ ።

፩ሺ፯፻፶፭ ራብዕ ፡ በስ ፡ ዘ፲ወ፯ቱ ፡ እመ ፡ ፈቀደት ፡ ብእሲት ፡ ዘማዊት ፡ ከመ ፡ ትነስሕ ፡ ትወልጥ ፡ አልባሲሃ ፡ ወታሰስል ፡ ሠርጐ ፡ ዝሙታ ፡ ወትቁም ፡ ዓመተ ፡ ፍጹመ ፡ እንዘ ፡ ይምዕድዋ ፡ ውስተ ፡ አንቀጽ ፡ አምቅድመ ፡ ትደለው ፡ ለተሳትፎ ፡ ምስለ ፡ መርዔተ ፡ ክርስቶስ ። ወእምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ ትቁም ፡ ካዕበ ፡ ፰ተ ፡ አውራኀ ፡ እንዘ ፡ ትሰምዕ ፡ ቃላተ ፡ ወትወፅእ ፡ ምስለ ፡ ንኡሰ ፡ ክርስቲያን ፡ ወ፩ተ ፡ አውራኀ ፡ ቀዊማ ፡ ምስለ ፡ ምእመናት ፡ ወእምድኅረ ፡ ፍጻሜ ፡ ዓመት ፡ ትትመጠው ፡ እምሥጢር ፡ ቅዱስ ። ወለእመስ ፡ ኮነት ፡ ዘኢተጠምቀት ፡ ወፈተወት ፡ ከመ ፡ ትነስሕ ፡ እምዝሙታ ፡ ይገሥጽዋ፡ ፵ ፡ መዋዕለ ፡ ወይትሐበይዋ ፡ ወትጠመቅ ።

፩ሺ፯፻፶፮ ሥርዋጽ ፡ ሕገ ፡ ገሞራውያን ፡ ይንበሩ ፡ በኵሉ ፡ ሕይወቶሙ ፡ ምስለ ፡ መስተብቍዓን ።

፩ሺ፯፻፶፯ ኃምስ ፡ ዕንቅራ ፡ ዘ፲ወ፰ቱ ፡ ወዘይዜሙ ፡ በእንስሳ ፡ ወኵሉ ፡ ዘይገብር ፡ ኃጢአተ ፡ ቅድመ ፡ ይብጻሕ ፡ ኅበ ፡ ፳ ፡ ዓመት ፡ ሰበ ፡ ነበሩ ፡ ፲ወ፭ተ ፡ ዓመተ ፡ እንዘ ፡ ይትጌሠጹ ፡ ይሳተፍዎሙ ፡ በጸሎት ፡ እምድኅረ ፡ ፲ወ፭ቱ ፡ ዓመት ፡ ወይትመጠዉ ፡ እምሥጢር ፡ ቅዱስ ፡ እምድኅረ ፡ ሐተቱ ፡ ግብሮሙ ።

፩ሺ፯፻፶፰ ሳድስ ፡ ረስጠጅ ፡ ፵ወ፱ቱ ፡ ዘይበልዕ ፡ ምስለ ፡ ዘማውያን ፡ ይትገኃሥ ፡ ወእመአኮ ፡ ይሰደድ ።

ስለ ፡ ዝሙት ፡ ቅጣት ።

ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ መዓርጉ ፡ አይመለስ ። እርሱ ፡ ከአመንዝራይቱ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሁኗልና ።

፩ሺ፯፻፶፪ ፫ኛው ። ጋብቻቸው ፡ ከተከለከለ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ስለሚሰስን ፡ ሰው ፡ ይናገራል ። በስ ፡ ፳፱፡ በሚስቱ ፡ ልጅ ፡ ያመነዘረ ፡ ፲፰ ፡ ዓመት ፡ ይለይ ። ፯ ፡ ዓመት ፡ እያለቀሰ ፡ ፩ ፡ ዓመት ፡ ቃለ ምዕዳን ፡ እየሰማ ፡ ፰ ፡ ዓመት ፡ ከምእመናን ጋር ፡ ቆሞ ።

፩ሺ፯፻፶፫ ፳፬ ። በሚስቱ ፡ እኅት ፡ የሚያመነዝር ፡ ፲፱ ዓመት ፡ ይለይ ። በሁለት ፡ ወንድማማቾች ያመነዘረች ፡ ሴትም ፡ እንደዚሁ ።

፩ሺ፯፻፶፬ ፳፭ ። ሁለት ፡ እትማማቾችን ፡ ያገባ ፡ እንደ ዚሁም ፡ ሁለት ፡ ወንድማማቾችን ፡ ያገባች ፡ ሴት ፡ ይለዩ ። በዕኑ ፡ ቀኖናም ፡ ይቀጡ ። በዚህ፡ ሳሉም ፡ አይገናኙዋቸው ።

፩ሺ፯፻፶፭ ፬ኛ ። በስ ፡ ፲፯ ፡ አመንዝራ ፡ ሴት ፡ ልት መለስ ፡ ብትወድ ፡ የዝሙት ፡ ጉጢን ፡ ጥላ ፡ ልብሱዋን ፡ ትለውጥ ። ከክርስቶስ ፡ መንጋዎችም ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ለመሆን ፡ ከመብቃቷ ፡ በፊት ፡ እየመከሯት ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ በአፍአ ፡ ትቁም ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ምዕዳን ፡ ሰምታ ፡ ከንኡስ ፡ ክርስቲያን ፡ ጋር ፡ እየወጣች ፡ ፰ ፡ ወር ፡ ትቆይ ። ፩ ፡ ወርም ፡ ከምእመናት ፡ ሴቶች ጋራ ፡ እየቆመች ፡ ቆይታ ፡ ከአንድ ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ ከቅዱስ ፡ ቁርባን ፡ ትቀበል ። ያልተጠመቀች ፡ ብትሆን ፡ ግን ፡ ከዝሙትዋም ፡ ልትመለስ ፡ ብትወድ ፡ ፵ ፡ ቀን ፡ ይምከርዋት ። ያስተምርዋትናም ፡ ትጠመቅ ።

፩ሺ፯፻፶፮ ሥርዋጽ ። ግብረ ፡ ሰዶም ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎች፡ በዘመናቸው ፡ ሁሉ ፡ ከአማላጆች ፡ ጋራ ፡ ይኑሩ

፩ሺ፯፻፶፯ ፭ኛ ። ዕንቅራ ፡ ፲፰ ። በእንስሳ ፡ የሚያመነዝር ፡ ፳ ፡ ዓመት ፡ ከመሙላቱ ፡ አስቀድሞ ፡ ኃጢአት ፡ የሠራ ፡ ሁሉም ፡ ፲፭ ፡ ዓመት ፡ ሲመከሩ ፡ ቆይተው ፡ ከ፲፭ ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ በጸሎት ይገናኙዋቸው ። ሥራቸውንም ፡ ከመረመሩ ፡ በኋላ ፡ ከቅዱስ ፡ ቍርባን ፡ ይቀበሉ ።

፩ሺ፯፻፶፰ ፮ኛ ። ረስጠጅ ። ፵፱ ። ከአመንዝሮች ፡ ጋራ ፡ የሚበላ ፡ ይከልከል ። ያለዚያም ፡ ይለይ ።

## አንቀጽ ፡ ፵፪ ።

፩ሺ፯፻፳፱ ጠስ ፡ ሀወ፱ቱ ፡ እለ ፡ ይነድኢ ፡ መርዔተ ፡ ዘኢኮነ ፡ ሎሙ ፡ በቀዳሚ ፡ ጊዜ ፡ ይጌሥፅዎሙ፡ ወበዳግም ፡ ይስድድዎሙ ፡ ወበሣልስ ፡ ይመትሩ ፡ እደዊሆሙ ፡ ወመርዔት ፡ ይግባእ ፡ ኀበ ፡ እግዚኡ ።

፩ሺ፯፻፴ ሣልስ ፡ ጠስ ፡ ዘ፴ወ፱ቱ ፡ ወዘይከወን ፡ መኳንንት ፡ ፈያት ፡ ቀታሊ ፡ ትትመተር ፡ እደዊሁ ፡ ወእደው ፡ እለ ፡ ይረድእዎ ። ወለእለሂ ፡ ይሰርቁ ፡ እምትዕይንት ፡ እመ ፡ ኮነ ፡ ዘሰረቅዎ ፡ እምንዋየ ፡ ሐቅል ፡ ባሕቲቱ ፡ ይዘብጥዎሙ ፡ ዘብጠተ ፡ ማሕመሚ ፡ ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ እምእንስሳ ፡ ይመትሩ ፡ እደዊሆሙ ። ወእለሂ ፡ ይሰርቁ ፡ እምሀገር ፡ ፍጹ ፡ ግዜ ፡ እመ ፡ ኮኑ ፡ አብዕልተ ፡ ወአማዕዝያን ፡ ይፍድዩ ፡ ካዕበተ ፡ ለእግዚአ ፡ ንዋዩ ፡ እመሰ ፡ ኮኑ ፡ ነዳያን ፡ ይዘብጥዎሙ ፡ ወይስድድዎሙ ፡ እመሰ ፡ ደገሙ ፡ ሰሪቀ ፡ ይመትሩ ፡ እደዊሆሙ ።

፩ሺ፯፻፴፩ መጽ ፡ ፻፲ወ፰ቱ ፡ ወሰረቅተ ፡ ሌሊትኒ ፡ እለ ፡ ይመጽኡ ፡ ኀበ ፡ ቤት ፡ ምስለ ፡ ንዋየ ፡ ሐቅል ። ወሰረቅተ ፡ መዓልትኒ ፡ መደንግፃን ፡ ወእለ ፡ ይፈትሑ ፡ አሕባለ ፡ ወእለ ፡ ይሰብሩ ፡ ቍልፋተ ፡ ይትገሠጹ ፡ እምአዝማዲሆሙ ፡ ወይፍድዩ ፡ ንዋየ ።

፩ሺ፯፻፴፪ ዘ፻፳ወ፪ቱ ፡ ወእለ ፡ ይከርዩ ፡ አብያተ ፡ እስመ ፡ ሕግ ፡ ትእዝዝ ፡ ኵነኔ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ እመሂ ፡ በሞት ፡ አው ፡ በተስዶ ፡ አው ፡ በንሢእ ፡ ንዋይ ።

፩ሺ፯፻፴፫ ራብዕ ፡ መጽ ፡ ፳ወ፩ዱ ፡ ወዘአስሐቶ ፡ ወሢጠ ፡ ለገብር ፡ ዘኢኮነ ፡ ሎቱ ፡ ወሰወሮ ፡ ይግባእ ፡ ኀበ ፡ እግዚኡ ፡ አው ፡ ሢጠ ፡ ዚአሁ ፡ አው ፡ አምሳሊሁ ።

፩ሺ፯፻፴፬ ጠስ ፡ ፵ወ፱ቱ ፡ ወእግዚአ ፡ ገብር ፡ ሰራቂ ፡ ይፈዲ ፡ ዘሰረቀ ፡ በዘስኩየ ፡ በእንቲአሁ ። ወለእመ ፡ ኢፈቀደ ፡ ይግባእ ፡ ሎቱ ፡ ገብረ ፡ ዚአሁ ፡ ለዘተሰርቀ ፡ ንዋዩ ፡ ይኩኖ ፡ ገብረ ፡ ለግሙራ ። ወዘሂ ፡ ተመጠወ ፡ እምእዴ ፡ ገብር ፡ ምንተኒ ፡ ዘተሰርቀ ፡ ይግባእ ፡ ኪያሁ ፡ ወ፬ተ ፡ እዴ ፡ ምክዕቢተ ። ወበንሥአ ፡ ገብረ ፡ ጕያዩ ፡ እምእግዚኡ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይግባእ ፡ ኪያሁ ፡ ወከልኤተ ፡ ዘከማሁ ፡ አው ፡ ፳ ፡ ዲናረ ።

፩ሺ፯፻፴፭ ወዘሂ ፡ የሀይድ ፡ ንዋየ ፡ በጊዜ ፡ ውዕየተ ፡

## ስለ ፡ ሌቦች ፡ ቅጣት ።

፩ሺ፯፻፳፱ ጠስ ፡ ፴፱ ። የእነርሱ ፡ ያልሆነውን ፡ መንጋ የሚነዱትን ፡ ሰዎች ፡ በመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ ይግረፉዋቸው ። በሁለተኛውም ፡ ጊዜ ፡ ያባርሯቸው ። በሦስተኛው ፡ እጃቸውን ፡ ይቁረጡዋቸው ፡ መንጋውም ፡ ወደጌታው ፡ ይመለስ ።

፩ሺ፯፻፴ ፫ኛ ፡ ጠስ ፡ ፴፱ ። ነፍስ ፡ ገዳይ ፡ የሆኑ ፡ የሽፍቶች ፡ አለቃ ፡ እጁ ፡ ትቈረጥ ። የሚረዱትም ፡ ሰዎች ፡ እጆች ። ከከተማ ፡ የሚሰርቁ ፡ ሰዎች ፡ የሰረቁት ፡ ከጦር ፡ መሣሪያ ፡ ወገን ፡ ብቻ ፡ ቢሆን ፡ ጽኑ ፡ ግርፋት ፡ ይግረፏቸው ። ከእንስሳ ፡ ወገን ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ እጃቸውን ፡ ይቍረጧቸው ። ከሀገርም ፡ (ከገጠርም) ፡ ፩ ፡ ጊዜ ፡ የሰረቁ ፡ ሰዎች ፡ ባለጸጎችና ፡ ራሳቸውን ፡ የቻሉ ፡ ቢሆኑ ፡ ለባለ ፡ ገንዘቡ ፡ በእጠፌታ ፡ ይክፈሉ ፡ ድሆች ፡ ቢሆኑ ፡ ግን ፡ ገርፈው ፡ ይሰደዷቸው ። ደግመው ፡ ቢሰርቁ ፡ ግን ፡ እጃቸውን ፡ ይቍረጧቸው ።

፩ሺ፯፻፴፩ መጽ ፡ ፻፲፰ ። የጦር ፡ መሣሪያ ፡ ይዘው ፡ ወደቤት ፡ የሚመጡ ፡ የሌሊት ፡ ሌቦችም ፡ ሞት ፡ ይገባቸዋል ። የሚያስደነግጡ ፡ የቀን ፡ ሌቦችም ፡ ልባብ ፡ የሚያወልቁ ፡ ቁልፍም ፡ የሚሰብሩ ፡ በዘመዶቻቸው ፡ ይመከሩ ። ገንዘቡንም ፡ ይክፈሉ ።

፩ሺ፯፻፴፪ ፻፳፪ ። ቤት ፡ የሚምሱ ፡ ሰዎችም ፡ በሞት ፡ ወይም ፡ በስደት ፡ ወይም ፡ ገንዘብ ፡ በመክፈልም ቢሆን ፡ ሕጎችን ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ቅጣትን ፡ ታዝዛለች ፡ እኮን ።

፩ሺ፯፻፴፫ ፬ኛ ፡ መጽ ። ገንዘቡ ፡ ያልሆነውን ፡ ባሪያ ፡ አባብሎ ፡ የሸጠው ፡ የደበቀውም ፡ ወደጌታው ፡ ይመልሰው ። ወይም ፡ ዋጋውን ፡ ወይም ፡ መሰሉን ፡ ይመልስ ።

፩ሺ፯፻፴፬ ጠስ ፡ ፵፱ ። የሌባ ፡ ባሪያ ፡ ጌታ ፡ በተከሰሰበት ፡ የሰረቀውን ፡ ስለእርሱ ፡ ይክፈል ። (ሊከፍል) ፡ ባይወድም ፡ ለዘለዓለም ፡ ባሪያ ፡ ይሆነው ፡ ዘንድ ፡ የራሱን ፡ ባሪያ ፡ ገንዘቡ ፡ ለተሰረቀበት ፡ ሰው ፡ ይስጠው ። የተሰረቀውን ፡ ገንዘብ ፡ ማናቸውንም ፡ ከባሪያው ፡ እጅ ፡ የተቀበለ ፡ በደኑቱን ፡ ፬ ፡ ዕፅፍ ፡ አድርጎ ፡ ይክፈል ። ከጌታው ፡ የኮበለለውን ፡ ባሪያ ፡ የተቀበለ ፡ ሰው ፡ እርሱን ፡ ሌላም ፡ እንደርሱ ፡ ያለ፡ ወይም ፡ ኻያ ፡ ዲናር ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፯፻፴፭ በእሳት ፡ ቃጠሎ ፡ ጊዜ ፡ ወይም ፡ ከፈረሰ ፡ ቤት፡

አንቀጽ ፡ ፶ ።

እሳት ፡ እው ፡ እምን ፡ ዘወድቀ ፡ ቤት ፡ እው ፡ እምይትመውት ፡ ባሕር ፡ ወእለሂ ፡ ይትሜጠዉ ፡ ዘንተ ፡ እምንግእሁ ፡ በዮሕሉት ፡ ይደልዎሙ ፡ ይፍድዩ ፡ ፬ተ ፡ እደ ፡ ለዘሂደሆ ፡ እስከ ፡ ሰዶሚ ፡ ዓመት ፡ ወለእመ ፡ ተዐደወ ፡ እምዓመት ፡ ይኩን ምክዕቢተ ።

፩ሺ፱፻፸፩ ወዘሂ ፡ ተማየጠ ፡ ግብረ ፡ ግሁዘ ፡ እንዘ ፡ የአምር ወሜጠ ፡ እው ፡ ወሀቦ ፡ ለካልእ ፡ እው ፡ ለትልወት ፡ እንስት ፡ እው ፡ ለጸባሕት ፡ ወእም ከመ ፡ ተከሥተ ፡ በላዕሌሁ ፡ ፩ዱ ፡ እምእሉ ፡ ግብራት ፡ ይምትሩ ፡ እደዊሁ ።

፩ሺ፱፻፸፪ ኃምስ ፡ ወእለሂ ፡ ይነሥኡ ፡ አልባስ ፡ ምዉታን ፡ እምውስተ ፡ መቃብሪሆሙ ፡ ይምትሩ ፡ እደዊሆሙ ፡ ወባሕቱ ፡ ከልእ ፡ ሕግ ፡ መተረ ፡ ፪ቱ ፡ እእዳው ፡ ወእእጋር ፡ ኅቡረ ።

፩ሺ፱፻፸፫ ወዳግማዊ ፡ መንፈሳዊ ፡ ረስጠጅ ፡ ዘ፳ወ፱ቱ ፡ ረስጠብ ፡ ፶ ፡ እመቦ ፡ ካህን ፡ እው ፡ ሕዝባዊ ፡ ዘሰረቀ ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቅብእ ፡ እው ፡ ስምእ ፡ ይሰደድ ፡ ወያግብእ ፡ ዘነሥአ ፡ ፭ተ ፡ እደ ፡ ምክዕቢተ ።

ስለ ፡ ስካርና ፡ ስለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ኃጢአቶች ።

ወይም ፡ በባሕር ፡ መስጠም ፡ ጊዜ ፡ ገንዘብ ፡ የሚቀማ ፡ ከነጣቂውም ፡ ይህን ፡ በተንኮል ፡ የሚቀበሉ ፡ ሰዎች ፡ የተቀበሉትን ፡ ገንዘብ ፡ እስከ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ አራት ፡ ዕጥፍ ፡ አድርገው ፡ ሊከፍሉ ፡ ይገባቸዋል ። ከአንድ ፡ ዓመትም ፡ ቢያልፍ ፡ ስምንት ፡ ዕጥፍ ፡ ይሁን ።

፩ሺ፱፻፸፩ ነፃ ፡ የወጣውን ፡ ባሪያ ፡ እያወቀ ፡ የገዛ ፡ የሸጠውም ፡ ወይም ፡ ለሌላ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ለሴቶች ፡ ትልወት ፡ ወይም ፡ ለግብር ፡ አሳልፎ የሰጠ ፡ ከእነዚህ ፡ ሥራዎች ፡ አንዱ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ከተገለጸ ፡ እጁን ፡ ይቁረጡት ።

፩ሺ፱፻፸፪ እምስተኛ ፡ ከመቃብራቸው ፡ ውስጥ ፡ አውጥተው ፡ የሙታንን ፡ ልብስ ፡ የሚወስዱ ፡ ሰዎች ፡ እጆቻቸውን ፡ ይቁረጡ ። ነገር ፡ ግን ፡ ፪ ፡ እጅንና ፡ ፪ ፡ እግርን ፡ በአንድነት ፡ መቁረጥን ፡ ሕግ ፡ ከልክሏል ።

፩ሺ፱፻፸፫ ሁለተኛው ፡ መንፈሳዊ ፡ ነው ። ረስጠጅ ፡ ፳፱ ፡ ረስጠብ ፡ ፶ ። ካህን ፡ ወይም ፡ ሕዝባዊ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዘይት ፡ ወይም ፡ ሰም ፡ የሰረቀ ፡ ቢኖር ፡ ይለይ ፡ የወሰደውንም ፡ እምስት ፡ ዕጥፍ፡ አድርጎ ፡ ይመልስ ።

---

## አንቀጽ ፡ ፶ ፡

በእንተ ፡ ስካር ፡ ወርደ ፡ ወወልድ ፡ ፀላዊ ፡ ወበእንተ ፡ ውጹት ፡ ውጉ ልቁ ፡ ኃጣውእ ።

፩ሺ፱፻፸፬ ቀዳሚ ፡ በእንተ ፡ ስካር ፡ ይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ "ዑቁ ፡ ወተዓቀቡ ፡ እምስካር" ፡ ወይቤ ፡ ከመ ፡ ይትኬነን ፡ ዘይበልዕ ፡ ወይሰቲ ፡ ምስለ ፡ ሰካርያን ፡ ነበ ፡ ሀሎ ፡ ብካይ ፡ ወሐቅየ ፡ ስነን ። ወጳውሎስኒ ፡ በውስተ ፡ መልእክቱ ፡ ለሰብእ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ይቤ ፡ "ከመ ፡ ኮሎሙ ፡ ሰካርያን ፡ ወተኃልያን ፡ ወዘማውያን ፡ እሙንቱ ፡ ኢይወርስዋ ፡ ለመንግሥቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወከልእ ፡ እምትድምሮቶሙ ፡ ወእም በሊዕ ፡ ምስሌሆሙ ። ወኢሳይያስኒ ፡ ነቢይ ፡ ይሁቦሙ ፡ ወይሌ ፡ ለሰካርያን ፡ ወይቤ ፡ "አሌ ፡ ሎሙ ፡ ለእለ ፡ ይገይሱ ፡ ወየሐውሩ ፡ ነበ ፡ ሰቴ ፡ ዘያሰክር ፡ ወይነብሩ ፡ ለሰትየ ፡ ወይን ፡ በተውኔት ፡ ወበማኅሌት ፡ እስከ ፡ ይመሲ ። ወሰሎሞንኒ ፡ ጠቢብ ፡ ወሀበ ፡ ወይሌ ፡ ውኁዘነ ፡ ወመቅ

## አንቀጽ ፡ ፶ ፡

ስለ ፡ ስካር ፡ ስለእረጣ ፡ ስለ ፡ ፀመፀኛ ፡ ልጅም፡ ስለ ፡ ነገር ፡ ሥራ ፡ ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ ቍጥር ፡ ይናገራል ።

፩ሺ፱፻፸፬ መጀመሪያ፡ ስለስካር ፡ ይናገራል ። ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ ከስካር ፡ እንድትጠበቁ ፡ ዕወቁ ፡ አለ ። (ሉቃ ፡ ፳፩ ፡ ፴፬) ፡ ከስካራሞች ፡ ጋራ ፡ የሚበላና የሚጠጣ ፡ ሰውም ፡ ልቅሶ ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨት ፡ ባለበት ፡ እንዲቀጣ ፡ ተናገረ ። (ማቴ ፡ ፳፬ ፡ ፵፺ - ፶፩) ። ጳውሎስም ፡ ለቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ፡ በጻፈው ፡ መልእክቱ ፡ ሰካራሞች ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዮች ፡ አመንዝራዎች ፡ እሊህ ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ እንዳይወርሱ ፡ ተናገረ ፡ ከአንድነታቸውና ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ከመብላትም ፡ ከለከለ ። (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፲) ። ነቢዩ ፡ ኢሳይያስም ፡ ወደሚያሰክር ፡ መጠጥ ፡ ገሥግሠዉ ፡ የሚሔዱ ፡ በዘፈንና ፡ በጫዋታ ፡ ወይን ፡ ለመጠጣት ፡ እስኪመሽ ፡ ድረስ ፡ የሚቀመጡ ፡ ወዮላቸው ፡ ብሎ ፡ ለሰካራሞች ፡ ልቅሶን ፡ ሰጥቷቸ

እንቀጽ ፡ ፶ ።

ሥርዓተ ፡ ወዘተሎ ፡ ምንዳቤያተ ፡ ለእለ ፡ ያበ ልፉ ፡ ስካረ ፡ ወይቤ ፡ "ኢትኩን ፡ ሰካሬ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ ለእመ ፡ አውተርከ ፡ ዓይንከ ፡ ኀበ ፡ እስተሐይጽ ፡ ጽዋዓት ፡ ወጽያሐት ፡ ተሐ ውር ፡ ዕራቁከ ፡ እስመ ፡ ይፀንዕ ፡ ለስካር ፡ የአሊ ፡ እምንስከተ ፡ ከይሲ" ። ወይቤ ፡ እስመ ፡ ስካር ፡ ይፈነውከ ፡ ኀበ ፡ ዝሙት ፡ ወዝሙትኒ ፡ ይወስደከ ፡ ኀበ ፡ ኃጕል ።

፩ሺ፯፻፸፩ ወናሁ ፡ ዘከሩ ፡ በአንቀጸ ፡ ካህናት ፡ ከመ ፡ ይደሉ ፡ በእንቲአሁ ፡ ተግሣጽ ፡ ኵንኔ ፡ መን ፈሳዊ ። ወዮሐንስ ፡ አፈ ፡ ወርቅ ፡ ሰመዮ ፡ ለስካር ፡ ዕበደ ፡ ፈቃዳዌ ፡ ወእዝልፎ ፡ ስካር ፡ ይከውን ፡ ፍኖተ ፡ ለኵሉ ፡ ምክንያተ ፡ ኃጢአት ፡ ወምንናት ። ወእዝልፎተ ፡ ስካርሰ ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ ውስተ ፡ መጻሕፍት ፡ ጠቢ ባን ፡ ያመጽእ ፡ ነቀዊቀጠ ፡ ወጥፍአተ ፡ ልብ ፡ ወኵብለ ፡ ወሞተ ፡ ግብት ፡ ወፈዘንተ ፡ ወውስ ዩተ ፡ ወቀኖስ ፡ አማሁት ፡ ወሕበጠ ፡ ናላ ፡ ወበእንተ ፡ ንቢብ ፡ ወወዲቀ ፡ እመካን ፡ ልዑል ፡ ወተወርዎ ፡ ውስተ ፡ ዓዘቅት ፡ ዕሙቅ ፡ ወው ስተ ፡ መካን ፡ ክሩይ ፡

፩ሺ፯፻፸፪ ወሰትዮ ፡ ወይንሰ ፡ በንዴተ ፡ በምክንያተ ፡ ፈውስ ፡ ናሁ ፡ አዘዘ ፡ ጳውሎስ ፡ ለጢሞቴዎስ ፡ ረድኡ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ "ጎዳጠ ፡ ወይነ ፡ ቍስሕ በእንተ ፡ ደዌከ ፡ ዘዘልፍ" ።

፩ሺ፯፻፸፫ ወበተዋናትሂ ፡ ይቤሉ ፡ ሐዋርያት ፡ ረስጣ ፰ ፡ ኀያል ፡ ወመዐትም ፡ ኢይሰተዩ ፡ ወይነ ፡ ከመ ፡ ኢያርስዕ ፡ ሰተበብ ፡ ወኢይትከሀሉ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ በርትዕ ። ወዘንቢሰ ፡ ዘንተ ፡ እኩ ፡ ንሕነ ፡ ዘንከልአሙ ፡ ከመ ፡ ኢይስተዩ ፡ ወይነ ፡ ለግሙራ ፡ እስመ ፡ ኢንክል ፡ ከመ ፡ ንመይን ፡ ዘፈጠረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለትፍሥ ሕተ ፡ ሰብእ ፡ አላ ፡ ንቤ ፡ ከመ ፡ ኢይስተዩ ፡ ብዙኀ ፡ ወኢይሰክሩ ። እስመ ፡ ኢይቤሉ ፡ መጻ ሕፍት ፡ ኢይስተዩ ፡ ወይነ ፡ አላ ፡ ይቤሉ ፡ ኢይስ ተዩ ፡ ወይነ ፡ ለስካር ፡ ወዘንተ ፡ ንቤሎሙ ፡ ለካህናት ፡ ወለመሣፍንትሂ ፡ ኀቡረ ።

፩ሺ፯፻፸፬ ዳግም ፡ በእንተ ፡ ርዴ ። በሕግ ፡ ተጻምዋ ፡ ከልአ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምንሣእ ፡ ርዴ ፡ ወዘ ሕግሰ ፡ ዳግሚያ ፡ አዘዘ ፡ ከመ ፡ ይለቅሕ ፡ ወኢ

ስዕ ፡ ስካርና ፡ ስለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ኃጢአቶች ።

ዋል ። (ኢሳ ፡ ፳ ፡ ፲፩ - ፲፫) ። ብልሁ ፡ ሰሎሞ ንም ፡ ልቅሶና ፡ ኀዘንን ፡ መቅሠፍትን ፡ መከራ ዎችንም ፡ ሁሉ ፡ ስካርን ፡ ለሚያዘወትሩ ፡ ሰጠ። እንዲህም ፡ አለ ፡ ስካራም ፡ አትሁን ። ጽዋዎችንና ኩባያዎችን ፡ ወደመመልከት ፡ ዓይንህን ፡ ብታ ዘወትር ፡ ዕራቁትህን ፡ ትሄዳለህና ። የስካር ፡ ፍጻሜዋ ፡ በእባብ ፡ ከመነከስ ፡ የሚከፋ ፡ ስለ ሆነ ። እንዲህም ፡ አለ ፡ ስካር ፡ ወደዝሙት ፡ ይወስድሀል ፡ ዝሙትም ፡ ወደጥፋት ፡ ይጠስድ ሀል ፡ አኮ ። (ምሳ ፡ ፳፫ ፡ ፳፱ - ፴፭) ።

፩ሺ፯፻፸፩ በአንቀጸ ፡ ካህናትም ፡ ስለእርሱ ፡ መንፈሳዊ ፡ ቅጣት ፡ እንዲገባ ፡ እነሆ ፡ ተናገሩ ። (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፻፳፩) ። ዮሐንስ ፡ አፈ ፡ ወርቅም ፡ ስካርን ፡ የፈቃድ ፡ ዕብደት ፡ ይለዋል ። ስካርን ፡ ማዘው ተርም ፡ ለኃጢአትና ፡ ለተናቀው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ምክንያት ፡ ይሆናል ፡ ስካርን ፡ ማዘውተርስ ፡ በፈላስፎች ፡ መጽሐፍ ፡ እንደተነገረ ፡ መንቀጥ ቀጥን ፡ የልብ ፡ ጥፋትን ፡ ሳንባ ፡ በሽታን ፡ በድ ንገት ፡ መሞትን ፡ ተቅማጥን ፡ መቃጠልን ፡ የአ ንጀት ፡ ድርቀትን ፡ (ቍስልን) ፡ የናላ ፡ ማበጥን፡ ለመናገር ፡ አለመቻልን ፡ ከፍ ፡ ካለ ፡ ቦታ ፡ መውደቅን ፡ ከጥልቅ ፡ ጕድጓድና ፡ ከተቆፈረ ፡ ጕድጓድ ፡ መውደቅንም ፡ ያመጣል ።

፩ሺ፯፻፸፪ በድንነት ፡ ምክንያት ፡ በመጠኑ ፡ ወይን ፡ መጠጣትንስ ፡ እነሆ ፡ ጳውሎስ ፡ ደቀ ፡ መዝ ሙሩ ፡ ጢሞቴዎስን ፡ ስለ ፡ ዘወትር ፡ ደዌህ ፡ ጥቂት ፡ ወይን ፡ ጨምር ፡ ብሎ ፡ አዝዞታል ። (፩ ፡ ጢሞ ፡ ፭ ፡ ፳፫) ።

፩ሺ፯፻፸፫ ሐዋርያትም ፡ በመጻሕፍት ፡ እንዲህ ፡ አሉ ። ረስጣ ፡ ፰ ። ኀይለኛና ፡ ቁጡ ፡ ሰው ፡ ጥበብን ፡ እንዳይረሳት ፡ ወይን ፡ አይጠጣ ። በእውነትም ፡ ሊፈርድ ፡ አይቻለውምና ። ይህን ፡ ማለታችን ፡ ግን ፡ ፈጽመን ፡ ወይን ፡ ከመጠጣት ፡ እኛ ፡ የም ንከለክላቸው ፡ አይደለንም ። እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሊደሰትበት ፡ የፈጠረውን ፡ ልንንቅ ፡ አን ችልምና ። ብዙ ፡ እንዳይጠጡና ፡ እንዳይሰክሩ ፡ ተናገርን ፡ እንጂ ። መጻሕፍት ፡ ለስካር ፡ ወይን ፡ አይጠጡ ፡ አሉ ፡ እንጂ ፡ ወይን ፡ አይጠጡ ፡ አላ ሉምና ። ይህንም ፡ ለካህናትና ፡ ለምእመናን ፡ በአንድነት ፡ እንነግራቸዋለን ።

፩ሺ፯፻፸፬ ሁለተኛው ፡ ስለእራጣ ፡ ይናገራል ። እግዚ አብሔር ፡ በመጀመሪያው ፡ ሕግ ፡ አራጣን ፡ ከለከለ ። (ዘፀ ፡ ፳፪ ፡ ፳፭) ። በሁለተኛው ፡ ሕግ፡

ይትረደዩ ። ወናሁ ፡ ተነግረ ፡ በቀኖናት ፡ ከመ ፡ ይኅድጉ ፡ ኪያሁ ፡ ወየሀቡ ፡ ንስሐ ፡ በእንቲአሁ ። ረስጠጅ ፡ ፵ወ ፱ቱ ፡ እመሂ ፡ እምካህናት ፡ ሆኑ ፡ ወሕዝባውያን ፡ ዘነሥአ ፡ ምንተኒ ፡ እምርደ ፡ ለያኅድግ ፡ ወእመ ፡ አከሰ ፡ ለያውፀር ።

፩ሺ፯፻፷፱ ዘኒቅያ ፡ በተፍጻሜቱ ፡ ኢትኩን ፡ መአብሰ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሶበ ፡ ትፈቅድ ፡ ነሢአ ፡ ርደ ፡ እምኢትከ ፡ ወለእመ ፡ ብከ ፡ ፍሬያት ፡ አው ፡ ወርቅ ፡ ወኢትፍቅድ ፡ ነሢአ ፡ ርደ ፡ እምኔሁ ፡ ወሚጥከ ፡ በብዙኅ ፡ ሚጠትከ ፡ ምኑነ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ ሀየንተ ፡ ነሢአ ፡ ርደ ፡ ነሣእከ ፡ ፫ተ ፡ አው ፡ ፬ተ ፡ እደ ፡ ካዕበተ ፡ ርዴ ።

፩ሺ፯፻፸ ፲ወ፯ቱ ፡ ወብዙኃን ፡ እለ ፡ ያፈቅሩ ፡ ለነሢአ ፡ ክፍል ፡ ዐቢይ ፡ ወረስዑ ፡ ቃለ ፡ ቅዱስ ፡ ዘይቤ ፡ "ወዘኢለቅሐ ፡ ወርቆ ፡ በርዴ" ። ለእለሰ ፡ ይነሥኡ ፡ ርዴ ፡ ይቤሎሙ ፡ ማኅበር ፡ ዐቢይ ፡ ለእመ ፡ ተረክበ ፡ ፩ዱ ፡ ዘያነሥእ ፡ ርደ ፡ አው ፡ ዘይገብር ፡ ካልአ ፡ ግብረ ፡ ዘከመዝ ፡ አው ፡ ዘይሌቅሕ ፡ ሥርናዮ ፡ በርዴ ፡ አው ፡ ዘይትመከነይ ፡ ቦቱ ፡ ተመክንዮተ ፡ በእንተ ፡ ነሢአ ፡ ረባኅ ፡ ርኩስ ፡ ይትመተር ፡ ወይረስይዎ ፡ ነኪረ ።

፩ሺ፯፻፸፩ ማልስ ፡ በእንተ ፡ ወልድ ፡ ዐላዊ ፡ መጽ ፡ ፰ቱ ፡ ይስድድዎ ፡ ለወልድ ፡ ዐላዊ ፡ እማእከለ ፡ ጉባኤ ፡ ወይሟእ ፡ እምርስቱ ፡ ወላድያኒሁ ፡ እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዘዘ ፡ በውስተ ፡ ብሊት ፡ ቀትለ ፡ ዚአሁ ፡ በውግረተ ፡ እብን ። ወሕግሰ ፡ ወሚሐዊት ፡ ተራኅርኅት ፡ ላዕሌሁ ፡ ወአዘዘት ፡ በዝንቱ ፡ ውሳኔ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ወልድ ፡ ዐላዌ ፡ ወዘየሐሥም ፡ ላዕለ ፡ ወላድያኒሁ ፡ ብዉሕ ፡ ሎሙ ፡ ከመ ፡ ይስድድዎ ፡ ሎቱ ፡ ወይንግሩ ፡ በቅድመ ፡ መኳንንት ፡ ወጉባኤ ፡ ስይጣ ፡ ዚአሁ ፡ እምወላድያኒሁ ፡ ወእምነ ፡ ርስቶሙ ።

፩ሺ፯፻፸፪ ራብዕ ፡ በእንተ ፡ ሠይጣት ። መጽ ፡ ፻፲ወ፰ቱ ፡ እመሂ ፡ ዘያስተዋድዮ ፡ ለሰብእ ፡ በምንትኒ ፡ እምግብር ፡ ሕሡም ፡ ያቅም ፡ ተሐብዮ ፡ ከመ ፡ ው



ግን ፡ አበድረው ፡ እንዳይቀበሉ ፡ አዘዘ ። (ሉቃ ፡ ፮ ፡ ፴) ። በመጻሕፍትም ፡ እርሱን ፡ እንዲተዉ ፡ ስለእርሱም ፡ ንስሐ ፡ እንዲሰጣቸው ፡ እነሆ ፡ ተነገረ ። ረስጠጅ ፡ ፵፱ ። ከካህናትና ፡ ከሕዝባውያን ፡ ከአራጣ ፡ ወገን ፡ ምንም ፡ ምን ፡ የተቀበለ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ይተው ። ባይተው ፡ ግን ፡ ይሻር ።

፩ሺ፯፻፷፱ ኒቅያ ፡ በመጨረሻው ። ከወንድምህ ፡ አራጣ ፡ መቀበልን ፡ በወደድህ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በደለኛ ፡ አትሁን ። እህል ፡ ወይም ፡ ወርቅ ፡ ቢኖርህ ፡ ከእርሱ ፡ አራጣ ፡ መቀበልን ፡ አትውደድ ። በብዙ ፡ ዋጋ ፡ ብትሸጠውም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የተናቅህ ፡ ትሆናለህ ። አንተ ፡ አራጣ ፡ ስለመቀበል ፡ ፈንታ ፡ ፫ ፡ ወይም ፡ አራት ፡ እጅ ፡ የአራጣ ፡ አጠፌታ ፡ ወስደሃልና ።

፩ሺ፯፻፸ ፲፯ ። ከፍ ፡ ያለውን ፡ ክፍል ፡ ለመውሰድ ፡ የሚፋጠኑ ፡ ወርቁን ፡ በአራጣ ፡ ያላበደረ ፡ የሚለውን ፡ ቅዱስ ፡ ቃል ፡ የረሱ ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ። አራጣ ፡ የሚቀበሉትንስ ፡ ታላቁ ፡ ጉባኤ ፡ አራጣ ፡ የሚቀበል ፡ ወይም ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሌላ ፡ ሥራ ፡ የሚሠራ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ስንዴውን ፡ በአራጣ ፡ የሚያበድር ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ርኩስ ፡ የሆነ ፡ ትርፍን ፡ ለማግኘት ፡ በዚህ ፡ ምክንያት ፡ የሚያመካኝ ፡ ሰው ፡ ቢገኝ ፡ ይለይ ። እንደ ፡ ባዕድም ፡ ያድርጉት ፡ ብሏቸዋል ።

፩ሺ፯፻፸፩ ፫ኛ ፡ ስለወንጀለኛ ፡ (ዓመፀኛ) ፡ ልጅ ፡ ይናገራል ። መጽ ፡ ፰ ። ወንጀለኛውን ፡ (ዓመፀኛውን) ፡ ልጅ ፡ ከጉባኤ ፡ ይለዩት ። ከወላጆቹም ፡ ርስት ፡ ይነቀል ። እግዚአብሔር ፡ በኦሪት ፡ በደንጋይ ፡ ተወግሮ ፡ እንዲሞት ፡ አዝዞአልና ። (ዘፀ ፡ ፳፩ ፡ ፲፯) ። ዘዳ ፡ ፳፩ ፡ ፲፰ - ፳፩) ። የክርስቶስ ፡ ሕግ ፡ ግን ፡ ለእርሱ ፡ ርኅራኄ ፡ አድርጋ ፡ ይህን ፡ ውሳኔ ፡ አዘዘች ። ልጅ ፡ ወንጀለኛ ፡ (ዓመፀኛ) ፡ ቢሆን ፡ በወላጆቹም ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ የሚሠራ ፡ ቢሆን ፡ ሊያባርሩት ፡ ይገባቸዋል ። ከወላጅነታቸውና ፡ ከርስታቸው ፡ መነቀሉን ፡ በዳኞችና ፡ በጉባኤ ፡ ፊት ፡ ይንገሩ ።

፩ሺ፯፻፸፪ ፬ኛ ። ስለ ፡ ነገር ፡ ሥራ ፡ ይናገራል ። መጽ ፡ ፻፲፰ ። ከክፉ ፡ ሥራ ፡ ወገን ፡ በማናቸውም ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ ነገር ፡ የሚሠራ ፡ ቢኖር ፡ ምስክ

አንቀጽ ፡ ፵፯ ።

ስለ ፡ ስካርና ፡ ስለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ኃጢአቶች ።

እሉ ፡ ያጸንዕ ፡ ቃሎ ፡ እሙን ፡ በእትዮሙ ፡ ሰማ ዕት ፡ ወምእመናን ፡ እደው ፡ ለውእቱ ፡ ብእሲ ። ወለእመ ፡ ኢክህለ ፡ ሳዕለ ፡ ዝንቱ ፡ ይፍዲ ፡ በአ ምጣነ ፡ ዘቦነ ፡ ይፈድዮ ፡ ለቢጹ ፡ ዝኩ ፡ ብእሲ ፡ እመ ፡ ተጠየቀ ፡ በላዕሌሁ ፡ ዝንቱ ፡ ግብር ፡ ወከ ማሁ ፡ ይኩን ፡ ኮነኔሁ ።

ሮችንና ፡ እውነተኞች ፡ ሰዎችን ፡ በመጥራት ፡ እ ውነተኛ ፡ ቃሉን ፡ እንዲሚያጸና ፡ ዋስ ፡ ይጥራ ፡ በ ዚህ ፡ ባይችል ፡ ፆ ፡ ሰው ፡ ለባልንጀራው ፡ ይከፍለ ው ፡ በነበረው ፡ ልክ ፡ ይክፈል ። ይህ ፡ ሥራ ፡ በእር ሱ ፡ ቢረጋገጥ ፡ ቅጣቱም ፡ እንደዚሁ ፡ ይሁን ።

፩ሺ፯፻፹፬ ድስት ፡ ፫ ፡ ወእምከመ ፡ ፈጸሕከሙ ፡ ዘእንበለ ፡ አድልዎ ፡ ተአምሮ ፡ ሐሰተ ፡ ዘእሁ ፡ ለዘይስተዋደዮ ፡ ለቢጹ ፡ በከንቱ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ፍሉን ፡ ይወድቅ ፡ በቃለ ፡ አፉሁ ፡ ወለዝንቱኒ ፡ መፍትው ፡ ከመ ፡ ይኩንንዎ ፡ ንጉሥ ፡ ወይግበሩ ፡ ቦቱ ፡ በከመ ፡ ውእቱ ፡ ፈቀደ ፡ ይግበር ፡ ዲበ ፡ ቢጹ ። ወለዘሰ ፡ ዘይ ሔስ ፡ ዲበ ፡ ቢጹ ፡ ኢትንድግዎ ፡ ዘእንበለ ፡ ኮንኔ ፡ ከመ ፡ ኢይትገበል ፡ ሳዕለ ፡ ንግር ፡ ከንቱ ፡ በዘየሐውር ፡ በፍኖት ፡ ርትዕት ፡ እው ፡ ከመ ፡ ኢይትገበል ፡ ካልእ ፡ ወኢይግበር ፡ በከመ ፡ ምግባሩ ፡ ወኢያድልዎ ፡ ለእኑ ፡ ከመ ፡ ይከ ሥት ፡ ዓቢየ ፡ አበሳ ፡ እኑሁ ፡ ወእመ ፡ አኮሰ ፡ ኢይሰምዖ ፡ እምኔሁ ፡ ወይንበር ፡ በስደት ።

፩ሺ፯፻፹፬ ድስቅ ፡ ፲ ። ያለአድልዎ ፡ ከፈረዳችሁ ፡ ባል ጀራውን ፡ በከንቱ ፡ የሚከሰውን ፡ ሰው ፡ ሐሰት ፡ ቃውቃላችሁ ። እርሱ ፡ በአነጋገሩ ፡ ፈጥኖ ፡ ይወድቃልና ። ይህንም ፡ ሰው ፡ በግልጥ ፡ ሊፈ ርዱበት ፡ ይገባል ። በባልንጀራውም ፡ ሊያ ደርግበት ፡ የወደደውን ፡ በእርሱ ፡ ያድርጉ በት ። በጓደኛውም ፡ ላይ ፡ ሐሰት ፡ የሚናገረ ውን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡ ቅጣት ፡ አትተዉት ። በቀናች ፡ መንገድ ፡ በሚሄደው ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ነገር ፡ እንዳይደፋፈር ፡ ወይም ፡ ሌላው ፡ እንዳ ይደፋፈር ፡ እንደ ፡ ሥራውም ፡ እንዳይሠራ ። ወንድም ፡ የወንድሙን ፡ ታላቅ ፡ በደል ፡ ሊገ ልጽ ፡ አይገባውም ። ያም ፡ ባይሆን ፡ ከእርሱ ፡ አይስሙ ። በስደትም ፡ ይኑር ።

፩ሺ፯፻፹፭ ኃምስ ፡ በአንቀጸ ፡ ሥራይ ። ጠስ ፡ ፺፱ ፡ ዘየአምር ፡ ለገባሬ ፡ ሥራይ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ያግብእ ፡ ለመሰፍን ፡ ወለእመ ፡ ኀብአ ፡ አሐዱ ፡ ወኢያግብኦ ፡ ለመኰንን ፡ ይደልዎ ፡ ለሎቱ ፡ ሥቃይ ፡ ዐቢይ ። ወእለ ፡ ይገብሩ ፡ እለሐዘረ ፡ በዘርናዕ ፡ ወይፈትዱ ፡ ቦቱ ፡ ይርብሑ ፡ ረባሐ ፡ በውእቱ ፡ ረቢሖት ፡ ፍትሕ ፡ ይዘብጥዎ ፡ ወይ ሰድዱ ።

፩ሺ፯፻፹፭ አምስተኛው ፡ ስለ ፡ ሥራይ ፡ ይናገራል ። ጠስ ፡ ፺፱ ። ሥራይ ፡ አድራጊውን ፡ የሚያው ቀው ፡ ሰው ፡ ለዳኛ ፡ ሊያቀርበው ፡ ይገባዋል ። አንድ ፡ ሰውም ፡ ደብቆ ፡ ባያቀርበው ፡ ጭንቅ ፡ ቅጣት ፡ ይገባዋል ። መንድግ ፡ በክንድ ፡ የሚያ ደርጉ ፡ በዚህም ፡ መስተፋቅር ፡ ጥቅምን ፡ ሊጠ ቀሙበት ፡ የሚወዱ ፡ ተገርፈው ፡ ይሰደዱ ።

፩ሺ፯፻፹፮ ሳድስ ፡ በአንቀጸ ፡ ውዕየት ፡ ዘንገሥት ፡ ፳፱ወ፬ቱ ፡ ዘአውደየ ፡ እሳተ ፡ ውስተ ፡ ሀገር ፡ እው ፡ በሐቅል ፡ እንዘ ፡ የኀሥሥ ፡ ኅክየተ ፡ ስብእ ፡ ዘእሃ ፡ ለየዐይ ።

፩ሺ፯፻፹፮ ስድስተኛ ፡ ስለቃጠሎ ፡ ይናገራል ። ፍትሐ ፡ ነገሥት ፡ ፳፱ ። የመንደሮችን ፡ ሰዎች ፡ ጉዳት ፡ ሽቶ ፡ በሀገር ፡ ወይም ፡ በዱር ፡ እሳት ፡ የጨመረ ፡ ሰው ፡ ይቃጠል ።

፩ሺ፯፻፹፯ ጠስ ፡ ፺፱ቱ ፡ ለእመ ፡ ተዐውቀ ፡ ፩ዱ ፡ ከመ ፡ አውዐየ ፡ ማኅደረ ፡ በእሳት ፡ በእእም ሮቱ ፡ ወበፈቃዱ ፡ ይትኰነን ፡

፩ሺ፯፻፹፯ ጠስ ፡ ፺፱ ። አንድ ፡ ሰው ፡ ዐውቆ ፡ በፈቃዱ ፡ ቤት ፡ እንዳቃጠለ ፡ ቢታወቅ ፡ ይቀጣ ።

፩ሺ፯፻፹፰ ወለእመ ፡ አውዐየ ፡ ፩ደ ፡ ዓፀደ ፡ በእኀብሮ ፡ ወወዕአ ፡ እሳት ፡ ወአውዐየ ፡ እብያተ ፡ ዘዓውዱ ፡ አልቦ ፡ ዕዳ ፡ ላዕለ ፡ ዘአውዐየ ፡ ቀዳሚ ።

፩ሺ፯፻፹፰ በመተባበር ፡ አንድ ፡ ቦታ ፡ ቢያቃጥል ፡ እሳትም ፡ ወጥቶ ፡ በዙሪያው ፡ ያለውን ፡ መን ደር ፡ ቢያቃጥል ፡ መጀመሪያ ፡ ባያያዘው ፡ ዕዳ ፡ የለበትም ።

፩ሺ፯፻፹፱ ወዘሂ ፡ ወደየ ፡ እሳተ ፡ ውስተ ፡ ገራህቱ ፡ ወሐረት ፡ እስከ ፡ አውዐየት ፡ ዘርአ ፡ ጎሩ ፡ ይሕ ትትዎ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘኢተዐቅበ ፡ በጽሉ ፡ ከሂሎቱ ፡ ከመ ፡ ኢያሐልቅ ፡ እሳት ፡ ጎበ ፡ መካን

፩ሺ፯፻፹፱ በእርሻው ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ያቀጣጠለ ፡ ሰው ፡ የጎረቤቱንም ፡ እዝመራ ፡ እስኪያቃጥል ፡ ድረስ ፡ ብትሄድ ፡ እሳት ፡ ወደሌላው ፡ ቦታ ፡ እንዳይተላለፍ ፡ በተቻለው ፡ ሁሉ ፡ ያልተጠነ

አንቀጽ ፡ ፶ ።

ካልእ ፡ ወይፍትሑ ፡ ላዕሌሁ ፡ ፍትሐ ፡ ሀካይ
ያን ፡ ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ ዘይትሀቀብ ፡ በኵሉ ፡
ግብር ፡ ሰበ ፡ ኀየሎ ፡ ነፍስ ፡ ወነፍሒ ፡ ለእሳት ፡
አልቦ ፡ ለዳ ፡ ላዕለ ፡ እንዳይ ፡ እሳት ፡

፩ሺ፯፻፹፱ ሳብእ ፡ በእንተ ፡ ኵሉ ፡ ኵልቈ ፡ አበሳት ።
ጠስ ፡ ፴ወ፰፡ ወለእመ ፡ ውስየ ፡ ሥጋ ፡ እግ
ዓዚ ፡ ይደልዎ ፡ ለፈታሒ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡
ላዕለ ፡ ገባሪ ፡ በእንተ ፡ ፈውሳት ፡ ወሥራሐት ፡
ወበእንተ ፡ ሕጸጸ ፡ መልክዕስ ፡ አልቦ ፡ እስመ ፡
ሥጋሁስ ፡ ለእግዓዚ ፡ ኢይትሜጠን ፡ በሤጥ ።
ወዘእውፀየስ ፡ እምሥጋ ፡ ገብር ፡ ይደልዎ ፡
ተኀሥሦ ፡ በዘእቅደምነ ፡ ዘክሮ ፡ በዘየሐጽጽ
እምሤጡ ።

፩ሺ፯፻፺ ዘ፴ወ፱ቱ ፡ ወዘሂ ፡ ይሞቅሕ ፡ እንስሳ ፡ ዘሰ
ኮነ ፡ ሎቱ ፡ ወይቀትሎ ፡ በኀጢአ ፡ መባልዕት ፡
አው ፡ በካልእ ፡ ፍና ፡ ይደልዎ ፡ ፈድየ ፡ ካለ
በት ፡ ሎቱ ።

፩ሺ፯፻፺፩ ወዘይትዔገል ፡ ምድረ ፡ አው ፡ ዘየፈልስ ፡
ደወለ ፡ ይደልዎ ፡ ያግብእ ፡ ካዕበቶ ፡ ለዘነሥአ ።

፩ሺ፯፻፺፪ ወመሐሃትኒ ፡ እለ ፡ የሀውኩ ፡ ጉባኤ ፡ እመ ፡
ሊቀ ፡ ሀገር ፡ ኮነ ፡ ነገሮሙ ፡ ወነበሩ ፡ ውስተ ፡
ስሕተቶሙ ፡ ይደልዎሙ ፡ ስደት ። ወለእመሰ ፡
ኮነንዎሙ ፡ ብዙኀ ፡ ጊዜያተ ፡ ወቆሙ ፡ ዳግመ፡
ውስተ ፡ ድፍረቶሙ ፡ ይዝብጥዎሙ ፡ ወይላጽዩ
ርእሶሙ ፡ ወያዝልፉ ፡ ነቢረ ፡ ውስተ ፡ ስደት ፡
ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ ሊቀ ፡ ዘኢአመሮሙ ፡ ይዝብጥ
ዎሙ ፡ በበትር ፡ ባሕቲቱ ፡ ወይኅድግዎሙ ።

፩ሺ፯፻፺፫ ወዘሂ ፡ ይገብር ፡ ማኅተመ ፡ በዲናራት ፡ ይም
ትሩ ፡ እደዊሁ ።

፩ሺ፯፻፺፬ ሳምን ፡ መጽ ፡ ፲ወ፱ቱ ፡ ወዘሂ ፡ ተዐደወ ፡
ላዕለ ፡ ካህን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይዝብጥዎ ፡
ወይሰድድዎ ፡ ወዘሂ ፡ ተዐደወ ፡ ላዕለ ፡ ዘተማኅ
ፀነ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወዘአውፅኦ ፡ እም
ኔሁ ፡ በኀይል ፡ ይትቀሠፍ ፡ ፲ወ፪ተ ፡ ጊዜ
ያተ ፡ ወይትአኀዝ ፡ በዘይደሉ ፡ በእንተ ፡ ጕያዪ ፡
ዘተማኅፀነ ፡ ኀቢሃ ። ወባሕቱ ፡ ይትመጠውዎ ፡
ካህን ፡ ወሰብእ ፡ ፈራህያነ ፡ እምእኑግ ፡ ሕዝ
ብ ፡ ወይክሥቱ ፡ ምክንያቶ ፡ ጕያዬቱ ፡ ወይፍ
ትሑ ፡ ላዕሌሁ ፡ በከመ ፡ አዘዘ ፡ ሕግ ።

፩ሺ፯፻፺፭ ሥርዋጽ ፡ ወከሓድያን ፡ ዘንዋ ፡ ይትረከቡ ፡

ስለ ፡ ስካርና ፡ ስለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ኃጢአቶች ።

ቀቀ ፡ ቢሆን ፡ ይመርምሩት ። በችልተኛችም ፡
ፍርድ ፡ ይፍረዱበት ። በሥራዉ ፡ ሁሉ ፡ የተጠ
በቀ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ነፋስም ፡ አያሎ ፡ እሳቱን ፡
ቢያናድደው ፡ እሳቱን ፡ ባያያዘው ፡ ሰው ፡ ዕዳ ፡
የለበትም ።

፩ሺ፯፻፹፱ ሰባተኛ ፡ ስለበደሎች ፡ ሁሉ ፡ ቊጥር ፡
ይናገራል ። ጠስ ፡ ፴፰ ። የጨዋ ፡ ልጅ ፡ አካል ፡
በእሳት ፡ ቢቃጠል ፡ ዳኛ ፡ በአድራጊው ፡ ላይ ፡
ስለ ፡ መድኃኒትና ፡ ስለ ፡ ሥራው ፡ (ለመድኃ
ኒት ፡ ስለከፈለውና ፡ ሥራ ፡ ስለፈታበት) ፡ ሊፈ
ርድ ፡ ይገባዋል ። ስለ ፡ አካል ፡ ጉድለት ፡ ግን ፡
የለም ። የጨዋ ፡ ልጅ ፡ አካል ፡ ዘዋጋ ፡ አይገመ
ትምና ። የባሪያ ፡ አካል ፡ ያቃጠለ ፡ ግን ፡ አስቀ
ድመን ፡ እንደተናገርን ፡ ከዋጋው ፡ በሚጎ
ድል ፡ መፈላለግ ፡ ይገባል ።

፩ሺ፯፻፺ ፴፱ ። ገንዘቡ ፡ ያልሆነውን ፡ እንስሳ ፡ አሥሮ፡
ምግብ ፡ በመከልከል ፡ ወይም ፡ በሌላ ፡ መን
ገድ ፡ የገደለው ፡ ለባለቤቱ ፡ ዕጥፍ ፡ አድርጎ ፡
መክፈል ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፯፻፺፩ ምድር ፡ የሚጋፉ ፡ ወይም ፡ ድንበር ፡ የሚ
ያፈርስ ፡ የወሰደውን ፡ ዕጥፍ ፡ አድርጎ ፡ ሊመ
ልስ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ፯፻፺፪ ጉባኤን ፡ (ስብሰባን) ፡ የሚያውኩ ፡ ጎበዛዝ
ትም ፡ አገር ፡ አሳዳሪዉ ፡ ነግሯቸው ፡ በስሕተ
ታቸው ፡ ቢኖሩ ፡ ስደት ፡ ይገባቸዋል ። ብዙ ፡
ጊዜ ፡ ቀጥተዋቸው ፡ ዳግመኛ ፡ በድፍረታ
ቸው ፡ ቢጸኑ ፡ ይግረፋቸው ። ራሳቸውንም ፡
ይላጯቸው ። በስደት ፡ መኖርንም ፡ ያዘውትሩ።
ዳኛ ፡ ያላስጠነቀቃቸው ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ በበትር፡
ብቻ ፡ ይብደበው ፡ ይተዋቸው ።

፩ሺ፯፻፺፫ በዲናር ፡ ማኅተም ፡ የሚሠራ ፡ እጁን ፡ ይቈ
ረጡት ።

፩ሺ፯፻፺፬ ስምንተኛ ፡ መጽ ፡ ፲፱ ። በቤተ ፡ ክርስቲያኑ፡
አገልጋይ ፡ ላይ ፡ የተደፋፈረውንም ፡ ይግረፉት
ያባርሩትም ። በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የተማፀነው
ንም ፡ ሰው ፡ ተደፋፍሮ ፡ በኀይል ፡ ከእርሱ ፡
ያወጣው ፡ ፲፪ ፡ ጊዜ ፡ ይገረፍ ። በእርሱዋ ፡ የተ
ማፀነውም ፡ ስለኮበለለ ፡ በሚገባ ፡ ይያዝ ። ነገር
ግን ፡ ካህኑና ፡ ከሕዝቡ ፡ ሽማግሌዎች ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ በሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ተቀብለው ፡ የሸ
ሸበትን ፡ (የደወለበትን) ፡ ምክንያት ፡ ይግለጡ።
ሕግም ፡ እንደሚያዝዘው ፡ ይፍረዱለት ።

፩ሺ፯፻፺፭ ሥርዋጽ ። (ከወላጆች) ፡ ከሞታቸው ፡ በኋላ፡

አንቀጽ ፡ ፶፩ ።

ወእምድኅረ ፡ ፍልሰቶሙ ፡ ኢይወርስዎሙ ፡ ለሰብእ ፡ ኢበጽሒፈ ፡ ትእዛዝ ፡ ወኢ ፡ ዘእንበለ ፡ ትእዛዝ ፡ ወለእመኒ ፡ ኮኑ ፡ አዝማዲሁ ፡ ኦርቶዶክሳውያን ፡ ዘእንበለ ፡ ባሕቲ ፡ ውሉዶሙ ፡ ለእመ ፡ ኮኑ ፡ ኦርቶዶክሳውያን ፡ እሉ ፡ የሀቡ ፡ ንዋዮሙ ፡ ለንጉሥ ። ወእለሂ ፡ ይትፈለጡ ፡ እምሃይማኖት ፡ ኢይከውኖሙ ፡ ጽሒፈ ፡ ትእዛዝ ፡ ወኢ ፡ ከመ ፡ የሀቡ ፡ ኢ ፡ በትእዛዝ ፡ ወኢ ፡ ዘእንበለ ፡ ትእዛዝ ፡ ወኢይረሱ ፡ ምንተኒ።

ስለ ፡ ጠንቋዮ ፡ ስለ ፡ ግዝረት ።

የሚገኙ ፡ ከሐዲዎችም ፡ ለአንዱስ ፡ እንኳ ፡ በማዘዣ ፡ ደብዳቤ ፡ ወይም ፡ ያለ ፡ ትእዛዝ ፡ አያውርሱዋቸው ። ዘመዶቹ ፡ ኦርቶዶክሳውያን ፡ ቢሆኑም ፡ ልጆች ፡ ብቻ ፡ ኦርቶዶክሳውያን ፡ ካልሆኑ ፡ ገንዘባቸውን ፡ ለንጉሥ ፡ ይስጡ ፡ እንጂ ። ከሃይማኖት ፡ የተለዩ ፡ ሰዎች ፡ ትእዛዝ መጻፍና ፡ በትእዛዝ ፡ ወይም ፡ ያለትእዛዝ ፡ ሊሰጡ ፡ አይገባቸውም ፡ እንዳችም ፡ አይውረሱ ።

## አንቀጽ ፡ ፶ወ፩ዱ ፡

በእንተ ፡ ሥዕርት ፡ ወግዝረት ፡ ወተአምኖ ፡ ወበእንተ ፡ ኵሉ ፡ ዘይደልዎ ፡ ለሊቅ ፡ ከመ ፡ ይወስክ ፡ ቦቱ ፡ ወያንትግ ፡ እምኔሁ ፡ በመዋዕሊሁ ፡ በከመ ፡ ይደሉ ፡ ለገቢር ፡ በትእዛዘ ፡ ቀኖናት ።

፩ሺ፯፻፺፯ ሥዕርትሰ ፡ ኢይደልዎሙ ፡ ለአይሁድ ፡ ከመ ፡ ያንትዉ ፡ ሥዕርቶሙ ፡ ወፈድፋደሰ ፡ ለዲያቆናት ፡ ወፀፍሮቶ ፡ ወእምኵሉ ፡ ዘየዐቢ ፡ ለካህናት ፡ እላ ፡ ይደሉ ፡ ላዕሌሆሙ ። ወዘኢይደሉሰ ፡ እንግልጽ ፡ ከመ ፡ ቃለ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ለሰብእ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ዘይቤ ፡ "ኢያሀውቀክሙኑ ፡ ፍጥረት ፡ በእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ከመ ፡ ለእመ ፡ አንኰ ፡ ብእሲ ፡ ሥዕርተ ፡ ርእሱ ፡ ኀሣር ፡ ውእቱ ፡ ሎቱ" ። ወበእንተ ፡ ዘእዘዘ ፡ በእንቲአሁ ፡ ለጢሞቴዎስ ፡ ረድኡ ፡ ገሥጾተ ፡ አንስት ፡ ከመ ፡ ይትገኃሣ ፡ እምተሠርግዎ ፡ በተፀፍሮ ፡ ሥዕርት ። ወበእንተ ፡ ዘከልአን ፡ እምኔሁ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሐዋርያ ፡ ዘይቤ ፡ በብዙኀሎቱ ፡ ኢትሠርገዋ ፡ በተፀፍሮ ፡ ሥዕርት ። ወለእመሰኬ ፡ ከልእዎን ፡ ለአንስት ፡ እምዝንቱ ፡ ግብር ፡ መጠን ፡ ይደልዎሙ ፡ ለአይሁ ፡ ተከልኦ ፡ እምኔሁ ።

፩ሺ፯፻፺፰ ወኢኀደግን ፡ ዘክሮተ ፡ እደው ፡ ምስለ ፡ አንስት ፡ በዝየ ፡ በእንተ ፡ ልማዶሙ ፡ በበይነ ፡ እሕሥሞ ፡ እስመ ፡ ልማዶሙ ፡ ወፍጥረቶሙ ፡ ፍሉጥ ፡ በአዝማንሙ ፡ ወናሁ ፡ ቦአ ፡ ተማሕጸነ ፡ እምነ ፡ ዝንቱ ፡ ዘይነግር ፡ ከሊአ ፡ ተሠርግዎ ፡ ሥጋዊ ።

፩ሺ፯፻፺፱ ወናሁ ፡ ስምዐ ፡ ኮነ ፡ ባስልዮስ ፡ ከመ ፡ ቃለ ፡ ሐዋርያ ፡ ውስተ ፡ ቀኖና ፡ ዘጸወሚት ፡ "ወይቤ ፡

## አንቀጽ ፡ ፶፭ ።

ስለጠጉርና ፡ ስለግዝረት ፡ ስለ ፡ መታመን ፡ በመጻሕፍት ፡ ትእዛዝ ፡ ለመሥራት ፡ ለዳኛ ፡ በዘመኑ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ሊጨምር ፡ ከእርሱም ፡ ሊያጎድል ፡ ስለሚገባውም ፡ ሁሉ ፡ ይናገራል ።

፩ሺ፯፻፺፯ ስለ ፡ ፀጉርስ ፡ ለወንዶች ፡ ፀጉራቸውን ፡ ሊያሳድጉ ፡ አይገባቸውም ። ይልቁንም ፡ ማሳደጉና ፡ መሠራቱ ። ከሁሉም ፡ የሚበልጥ ፡ ለካህናት ፡ ሊላጩት ፡ ይገባል ፡ እንጂ ። ማሳደጉ ፡ አለመገባቱስ ፡ ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ ለቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ፡ እንደተናገረው ፡ ነው ። ወንድ ፡ ጠጉሩን ፡ ቢያሳድግ ፡ ለእርሱ ፡ ተዋርዶው ፡ እንደሆነ ፡ ስለዚህ ፡ ፍጥረት ፡ አያሳውቃችሁምን ? (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፲፩ ፡ ፲፫ - ፲፭)። ለደቀመዝሙሩ ፡ ለጢሞቴዎስም ፡ ስለእርሱ ፡ ጠጉራቸውን ፡ በመሠራት ፡ ከማጌጥ ፡ ይርቁ ፡ ዘንድ ፡ ሴቶችን ፡ ማስማተርን ፡ ስለአዘዘ ፡ ነው ። ( ፩ ፡ ጢሞ ፡ ፪ ፡ ፱ - ፲ ) ። ሐዋርያ ፡ ጴጥሮስም ፡ ጠጉራችሁን ፡ በመሠራት ፡ አታጊጡ ፡ በማለቱ ፡ ከእርሱ ፡ ስለከለከላቸው ፡ ነው ። (፩ ፡ ጴጥ ፡ ፫ ፡ ፩ - ፮) ። ከዚህ ፡ ሥራ ፡ ሴቶችን ፡ ከከለከሉአቸው ፡ ለወንዶችማ ፡ ከዚህ ፡ ሥራ ፡ መከልከል ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ይገባቸው ፡ ይሆን !

፩ሺ፯፻፺፰ በዚህም ፡ ወንዶችን ፡ ከሴቶች ፡ ጋራ ፡ መጥቀስን ፡ አልተውንም ። ስለ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ልማዳቸው ። በዘመናቸው ፡ ልማዳቸውና ፡ ተፈጥሮዋቸው ፡ ልዩ ፡ ነበረና ። ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ሥጋዊ ፡ ጌጥን ፡ መከልከልን ፡ የሚናገር ፡ ምክር ፡ እነሆ ፡ ተሠራ ።

፩ሺ፯፻፺፱ እንደ ፡ ሐዋርያ ፡ ቃል ፡ በጾሙ ፡ ትእዛዝ ፡ ባስልዮስ ፡ እነሆ ፡ ምስክር ፡ ሆነ ። ሐዋርያ ፡

እንቀጽ ፡ ፶፩ ።

ኢይኅድግ ፡ ብእሲ ፡ ሥዕርቶ ፡ ከመ ፡ ይኑኅ ፡ ለግሙራ ፡ ከመ ፡ ቃለ ፡ ሐዋርያ ፡ ወይደሉ ፡ ሳጽ ዮቱ” ። ወከመ ፡ ቃለ ፡ ሐዋርያት ፡ በዋንተ ፡ ዲድስቅልያ ፡ ዘይቤሉ ፡ ኢታንኅ ፡ ሥዕርተ ፡ ርእስከ ፡ ወኢትሕፅኖ ፡ ወኢትቅብእ ፡ ዕፍረተ ፡ ወኢትኅድጎ ፡ ሰፉሐ ፡ ኢፍቱለ ፡ ወኢዕፉረ ፡ ወኢትረሲ ፡ ለከ ፡ ድንጉዛተ ፡ ወነኮላለ ፡ አላ ፡ ላጽዮ ፡ ወእጽሪ ፡ ርእሰከ ። ወኢትሠርገው ፡ በሠርጕ ፡ ዘትፈትወከ ፡ ባቲ ፡ ብእሲት ፡ ወት ከውን ፡ ኃጥአ ፡ በኃጢአታ ።

፩ሺ.፶፱ ፶፱ ወጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ናሁ ፡ ገብረ ፡ ዘንተ ፡ በርእሱ ፡ ፪ተ ፡ ጊዜያተ ፡ በከመ ፡ ስምዐ ፡ ኮነ ፡ መጽሐፈ ፡ አብረክሲስ ፡ ወ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ብፅዓት ፡ ኮነ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወብፅዐትሰ ፡ ዘእግዚ አብሔር ፡ ኢያከውን ፡ ዘእንበለ ፡ በገቢረ ፡ ትሩ ፋት ፡ ወፈድፋዶስ ፡ መኑ ፡ ከመ ፡ ዝንቱ ፡ ሐዋ ርያ ፡ ዘጽኑዕ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወበጽድቅ ። ወእልቦ ፡ ኑፋቄ ፡ ወካሕድ ፡ ከመ ፡ ገቢረ ፡ ብፅ ዐቱ ፡ ለሐዋርያ ፡ ትሩፍ ፡ ሕግ ፡ ኮነ ፡ ለዝሉፉ ፡ ለሰብእ ፡ ጽዋዔሁ ፡ ዘናሁ ፡ ገብረ ፡ ትሩፋተ ።

፩ሺ.፷፱ ወቃልኒ ፡ ዘተነግረ ፡ ውስተ ፡ ቀኖናተ፡ሆሙ ፡ ለጉባኤ ፡ ኒቅያ ፡ ዘኍላቍሆሙ ፡ ፫፻ ፡ እምድኅረ ፡ ፲፰ ፡ ዘይብል ፡ ኢያስተርኢ ፡ ሥዕርትከ ፡ በአ ፍአ ፡ እስመ ፡ ናሁ ፡ ሐዋርያ ፡ ከልአ ፡ ዘንተ ፡ አምሳለ ። ወኢትንጣእ ፡ እምጸጕረ ፡ ጽሕምከ ፡ ጊዜ ፡ ትላጺ ፡ ሥዕርተ ፡ ርእስከ ፡ ወኢትኅድግ ፡ ላዕሌከ ፡ ሥርጋዌ ፡ እምጸጕረ ፡ ርእስከ ።

፩ሺ.፷፱፩ ወጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ወጉባኤ ፡ ዘማንግሬ ፡ ሶበ ፡ ከልአዎን ፡ ለአንስት ፡ እምላጽዮ ፡ ጸጕ ሮን ፡ አዘዝዎን ፡ ለባሕቲቶን ፡ ዘእንበለ ፡ እደው ።

፩ሺ.፷፱፪ ወበእንተ ፡ ማዝረትሰ ፡ እምትእዛዘ ፡ ብሊት ፡ ውእቱ ፡ ተሠርዐ ፡ ከመ ፡ ይትፈለጡ ፡ ሕዝበ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምኵሉ ፡ አሕዛብ ፡ በከመ ፡ ይትኃተሙ ፡ እግብርት ፡ ለመላኪሆሙ ። ወበ እንተዝ ፡ ኢይደሉ ፡ ተሰምዮ ፡ ዘእንበለ ፡ እም ድኅረ ፡ ማዝረት ። ወይመርሕ ፡ ላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ ቃለ ፡ ሉቃስ ፡ በውስተ ፡ ወንጌል ፡ በእንተ ፡ ዮሐንስ ፡ ወእግዚእነ ፡ ዘይቤ ፡ መጽአ ፡ ኀበ ፡ ሕፃን ፡ ከመ ፡ ይግዝርዎ ፡ ወሰመይዎ ፡ ስሞ ።

ስለ ፡ ጠጕርና ፡ ስለ ፡ ግዝረት ።

እንደተናገረው ፡ ወንድ ፡ ከቶ ፡ ጠጕሩን ፡ ያድግ፡ ዘንድ ፡ አይተወው ። ሊላጨውትም ፡ ይገባል ፡ አለ ። በዲድስቅልያ ፡ መጀመሪያ ፡ እንደተነገ ረው ፡ እንደ ፡ ሐዋርያት ፡ ቃልም ፡ የራስህን ፡ ጠጕር ፡ አታሳድግ ። አትከባከበው ፡ ሽቱም ፡ አትቀባው ። ግልስልስ ፡ አታድርገው ፡ ወይም ፡ የተፈተለ፡ወይም፡የተጕነጐነ ፡ አድርገህ ፡ አት ተወው ። ሹርቢ፡ስርሜዶ ፡ አታድርግ ። ላጨው እንጂ ፡ ራስህንም ፡ አጥራ ። ሴት ፡ አንተን ፡ በም ትወድበት ፡ ጌጥ ፡ አታጊጥ ። በእርሱዋም ፡ ኃጢ አት ፡ አንተ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ትሆናለህ ።

፩ሺ.፶፱ ፶፱ ሐዋርያ ፡ ጳውሎስም ፡ እነሆ ፡ ይህን ፡ በራሱ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ አደረገ ፡ የሐዋርያት ፡ መጽሐፍ ፡ (ሥራ) ፡ እንደመሰከረ ፡ (የሐዋ ፡ ፲፰ ፡ ፲፰ ። ፳፩ ፡ ፳፬ ።) ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ ብፅዓት ፡ ነበ ረበትና ፡ ነው ። ለእግዚአብሔርም ፡ የሚሆን ፡ ብፅዓት ፡ ትሩፋት ፡ በመሥራት ፡ ካልሆነ ፡ በቀ ር ፡ አይሆንም ፡ ይልቁንም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስና፡ በእውነት ፡ እንደዚህ ፡ ሐዋርያ ፡ ያለ ፡ ማነው ? ፍጹም ፡ ሐዋርያ ፡ እሱን ፡ ትሩፋት ፡ አደርጎ ፡ የሠራው ፡ ብፅዓቱን ፡ መፈጸሙ ፡ ለጠራቸው ፡ ሰዎች ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ሕግ ፡ እንደሆነ ፡ ጥርጥ ርና ፡ ክህደት ፡ የለበትም ።

፩ሺ.፷፱ ከኸያ ፡ በኋላ ፡ ቍጥራቸው ፡ ኸያ ፡ በሚሆን ፡ በኒቅያ ፡ ጉባኤ ፡ መጻሕፍት ፡ የተነገረው ፡ ቃልም ፡ እንዲህ ፡ የሚል ፡ ነው ። ጠጕርህ ፡ በአፍአ ፡ (በውጭ) ፡ አይታይ ። ሐዋርያ ፡ ይህን፡ አርአያ ፡ ከልክሎአልና ። ራስህን ፡ በምትላጭበ ትም ፡ ጊዜ ፡ ከጽሕምህ ፡ ፀጉር ፡ አትንጣለት ። ከራስህ ፡ ፀጉርም ፡ ለጌጥ ፡ አትተውለት ።

፩ሺ.፷፱፩ ሐዋርያ ፡ ጳውሎስና ፡ የግንግራ ፡ ጉባኤ ፡ ሴቶ ችን ፡ ጠጕራቸውን ፡ ከመላጨት ፡ በከለከሏ ቸው ፡ ጊዜ ፡ ከወንዶች ፡ ለይተው ፡ ብቻቸውን ፡ አዘዟቸው ።

፩ሺ.፷፱፪ ስለ ፡ ግዝረትም ፡ ከብሉይ ፡ ትእዛዝ ፡ ወገን ፡ ነው ። ባሮች ፡ ለጌቶቻቸው ፡ እንደሚከተቡ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ወገኖች ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይለዩ ፡ ዘንድ ፡ ታዘዘ ። ስለዚህ ፡ ከግዝረት ፡ በኋላ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ስም ፡ ማውጣት ፡ አይገ ባም ። በዚህም ፡ ላይ ፡ ሉቃስ ፡ በወንጌል ፡ ስለዮ ሐንስና ፡ ስለጌታችን ፡ ይገዝሩት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ሕፃኑ ፡ መጡ ፡ ስሙንም ፡ አወጡለት ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ያስረዳል ። (ሉቃ ፡ ፩ ፡ ፶፱ ። ፪ ፡ ፳፩) ።

አንቀጽ ፡ ፶፭ ።

፩ሺ፰፻፫ ወሶበ ፡ አስተጋብአት ፡ ሕግ ፡ መሢሓዊት ፡ ኵሎ ፡ አሕዛበ ፡ ተጋብረት ፡ ለብእሲ ፡ ዘተፈጥረ ፡ በነፍስ ፡ ወሥጋ ፡ ተሰምየ ፡ መንፈሳዊት ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ ጥምቀት ፡ በዘባቲ ፡ ይትፈለጡ ፡ መሢሓውያን ፡ እምካልኣን ፡ ወረሰዩ ፡ ሎቱ ፡ ተሰምዮቶ ፡ ስሞሙ ፡ በጊዜ ፡ ጥምቀቶ ፡ ክርስትና ፡ በከመ ፡ ያወስኡ ፡ ወያንብሩ ፡ አጋእዝት ፡ ስመ ፡ ለአግብርቲሆሙ ።

፩ሺ፰፻፬ ወበእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ግብር ፡ በጽሐት ፡ ምክንያት ፡ ኀበ ፡ አዳም ፡ ብእሲት ፡ ቀዳማዊት ፡ ከመ ፡ ይሰምያ ፡ በእንተ ፡ ኵነኔቱ ፡ ኪያሃ ፡ ወእግዚእናሁ ፡ ላዕሌሃ ። ወበዝቱ ፡ ፍና ፡ በጽሑ ፡ ፍጥረት ፡ እንስሳ ፡ ኀበ ፡ አዳም ፡ ከመ ፡ ይሰምዮሙ ፡ ትእምርተ ፡ በእንተ ፡ ኵነኔቱ ፡ ኪያሆሙ ፡ ወእግዚእናሁ ፡ በላዕሌሆሙ ።

፩ሺ፰፻፭ ወበሕግስ ፡ ሐዲስ ፡ እስመ ፡ ግዝረት ፡ ኀበ ፡ ዘይትገበር ፡ እምበዓለ ፡ ግዝረት ፡ በከመ ፡ ፍና ፡ ልማድ ፡ እኮ ፡ እምፍና ፡ ቀኖና ፡ ሕጋዊ ። ወከመ ፡ ውእቱ ፡ ተነግረ ፡ ግብሩ ፡ ውስተ ፡ ኦሪት ፡ በሳምን ፡ ዕለት ፡ እምዕለተ ፡ ልደቱ ፡ ለዘይትገዘር ፡ ወይእቲ ፡ እመ ፡ ካልእ ፡ እምሳምንት ፡ ኢትትኈለቍ ፡ እምግዝረት ፡ ሕጋዊት ። ወእለ ፡ ይገብርዋ ፡ እምሰብአ ፡ ሐዲስ ፡ ሕግ ፡ ኢይገብርዋ ፡ በሳምን ፡ ዕለት ፡ ወኢየኀርዩ ፡ ዘንተ ።

፩ሺ፰፻፮ ወግዝረትሰ ፡ በኀቤነ ፡ ይደሉ ፡ ኀዲጎታ ፡ ወይደሉ ፡ ገቢሮታ ፡ ዘእንበለ ፡ ውሳኔ ፡ ዘሕግ ። ወትምህርተ ፡ ዝንቱ ፡ ቃል ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ በውስተ ፡ ምዕራፍ ፡ ሳብዕ ፡ እምነ ፡ መልእክቱ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኀበ ፡ ሰብአ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ወይቤ ፡ "ኢኮነ ፡ ግዝረት ፡ ምንተኒ ፡ ወቍልፈትኒ ፡ ዳእሙ ፡ ጽድቅስ ፡ ዐቂበ ፡ ትእዛዘ ፡ እግዚአብሔር ። ወብሂሎቱ ፡ ኀበ ፡ ሰብአ ፡ ገላትያ ፡ ዘኀምስ ፡ እምኔሃ ፡ "ተገዘርክሙ ፡ ኢይበቍዕ ፡ ወኢተገዘርክሙ ፡ አላ ፡ ሃይማኖት ፡ ዘይትፌጸም ፡ በፍቅር ። ወይገሙ ፡ ዘንተ ፡ ቃለ ፡ በክፍል ፡ ሳድስ ፡ እምኔሃ ፡ ወይቤ ፡ ኢኮነ ፡ ግዝረት ፡ ምንተኒ ፡ ወኢቍልፈት ፡ አላ ፡ በቍዔቱ ፡ ግብርስ ፡ ፍጥረት ፡ ሐዲስ ፡ ዘውእቱ ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትና ።

ስለ ፡ ጠጉርና ፡ ስለ ፡ ግዝረት ።

፩ሺ፰፻፫ የክርስቶስ ፡ ሕግ ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ በሰበሰበች ፡ ጊዜ ፡ በነፍስና ፡ በሥጋ ፡ ለተፈጠረ ፡ ሰው ፡ መንፈሳዊት ፡ ስም ፡ ተደረገች ። ይህችውም ፡ ክርስቲያኖች ፡ ከሌሎቻቸው ፡ የሚለዩባት ፡ ጥምቀት ፡ ናት ። የስሙ ፡ አወጣጥ ፡ በጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡ ጊዜ ፡ እንዲሆን ፡ አደረጉ ። ጌቶች ፡ ለባሮቻቸው ፡ ስም ፡ አውጥተው ፡ እንዲያኖሩ ።

፩ሺ፰፻፬ ስለዚህም ፡ ሥራ ፡ ምክንያት ፡ እርሱ ፡ እርሱዋን ፡ ስለሚገዛት ፡ ጌትነቱም ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ስለሆነ ፡ ስም ፡ ያወጣላት ፡ ዘንድ ፡ የቀደመችው ፡ ሴት ፡ ወደአዳም ፡ ሄደች ። በዚችም ፡ መንገድ ፡ ፍጥረተ ፡ እንስሳ ፡ እነርሱን ፡ ስለሚገዛቸው ፡ ጌትነቱም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ስለሆነ ፡ በምልክታቸው ፡ ስም ፡ ያወጣላቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አዳም ፡ መጡ ። (ዘፍ ፡ ፪ ፡ ፲፱ - ፳ ። ፫ ፡ ፳ ።)

፩ሺ፰፻፭ በሐዲስ ፡ ሕግ ፡ ግን ፡ ከገዛሪ ፡ የሚደረግ ፡ ግዝረት ፡ በልማድ ፡ ጎዳና ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሕጋዊ ፡ ከሆነ ፡ ከትእዛዝ ፡ ወገን ፡ አይደለም ። ሥርዓቱ ፡ የሚገዘረው ፡ ሰው ፡ ከተወለደበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ በስምንተኛው ፡ ቀን ፡ እንዲሆን ፡ በኦሪት ፡ እንደዚህ ፡ ተነገረ ። ከስምንት ፡ ቀን ፡ በሌላ ፡ ጊዜ ፡ የሆነች ፡ ግዝረት ፡ ከግዝረት ፡ ወገን ፡ ሕጋዊት ሁና ፡ አትቆጠርም ። ከሐዲሱ ፡ ሕግ ፡ ሰዎች ፡ ወገን ፡ የሚሠሩዋትም ፡ በስምንት ፡ ቀን ፡ አያደርጓትም ። ይህንም ፡ ዕለት ፡ አይመርጡም ።

፩ሺ፰፻፮ ግዝረት ፡ ግን ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ሊተዉት ፡ ይገባል ። ያለ ፡ ሕግ ፡ ውሳኔም ፡ ሊሠሩዋት ፡ ይገባል ። የዚህም ፡ ምልክቱ ፡ ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ ለቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ፡ በጻፈው ፡ በመጀመሪያ ፡ መልእክቱ ፡ በ፯ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ መገዘር ፡ ወይም ፡ አለመገዘር ፡ ምንም ፡ አይደለም ። ጽድቅስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ መጠበቅ ፡ ነው ፡ አለ ። (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፯ ፡ ፲፰ - ፳) ። ዳግመኛም ፡ ለገላትያ ፡ ሰዎች ፡ በጻፈው ፡ በ፭ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ የሚጠቅም ፡ በፍቅር ፡ የተፈጸመ ፡ ሃይማኖት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ መገዘርም ፡ አለመገዘርም ፡ አይጠቅምም ፡ ያለው ፡ ነው ። ይህንም ፡ ቃል ፡ ከእርስዋ ፡ በ፮ኛው ፡ ክፍል ፡ መገዘር ፡ ወይም ፡ አለመገዘር ፡ ምንም ፡ አይደለም ። የሚጠቅም ፡ ሥራ ፡ ሐዲስ ፡ ፍጥረት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ደገመው ። ይኸውም ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡

አንቀጽ ፡ ፃ፩ ።

፩ሺ፰፻፶፯ ወቃላቲሁስ ፡ እንተ ፡ ትትከሠት ፡ እምእፉሁ ፡ ትንግር ፡ ከሊአ ፡ ማዝረት ፡ እስመ ፡ ኮነ ፡ መፍቅዱ ፡ ባቲ ፡ ከሊአ ፡ እምተእንዞ ፡ በሕግ ፡ አራት ፡ ዘጥንተ ፡ ዚአሃ ፡ ትእዛዘ ፡ ማዝረት ። ወስመይ ፡ ሰሕግ ፡ በጥንተ ፡ ዚአሃ ፡ በከመ ፡ ተሰምዩ ፡ መጻሕፍት ፡ በጥንቶሙ ፡ ዘውእቶሙ ፡ መጽሐፈ ፡ ፍጥረት ፡ ወመጽሐፈ ፡ ኍልቍ ። ወበከመ ፡ ዝንቱ ፡ ፍኖት ፡ ተሰምየት ፡ ሕግ ፡ አራት ፡ በስመ ፡ ማዝረት ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ ዘዘከሩ ፡ ወተሰምየት ፡ ክልኤታ ፡ በቍልፈት ። ወዘይመርሕ ፡ ላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ ቃሉ ፡ ዘውስተ ፡ ምስራፍ ፡ ሳብዕ ፡ ለሰብእ ፡ ቆሮንቶስ ፡ "ለእመ ፡ ተጸውዐ ፡ ብእሲ ፡ ኅበ ፡ ሃይማኖት ፡ እንዘ ፡ ግዙር ፡ ውእቱ ፡ ኢይማባእ ፡ ኀበ ፡ ቍልፈት" ።

፩ሺ፰፻፶፰ ወአፍአሁ ፡ ለዝንቱ ፡ ቃል ፡ እመስ ፡ ውእቱ ፡ አመረ ፡ ኀበ ፡ ተግዝሮ ፡ በዝከር ፡ በሕግ ፡ ማዝረት ፡ ዘውእቱ ፡ መተረ ፡ ሥጋ ፡ ለምንትኑ ፡ ይቤ ፡ ኢይግባእ ፡ ኀበ ፡ ቍልፈት ፡ እስመ ፡ ኢይትከሀሎ ፡ ለግዙር ፡ ከመ ፡ ይትመየጥ ፡ ኀበ ፡ ከዊነ ፡ ኢግዙር ፡ ወይጸንዕ ፡ ዝንቱ ፡ ቃለ ፡ በመልእክቱ ፡ ኀበ ፡ ሰብእ ፡ ሮሜ ፡ በብሂሎቱ ፡ ለእመ ፡ እመንከ ፡ ኦ ፡ ብእሲ ፡ ወተዓቀብከ ፡ ሕገ ፡ አራት ፡ ይከውን ፡ ማዝረትከ ፡ ቍልፈተ ፡ ወእመሰ ፡ እንዘ ፡ ቈላፍ ፡ አንተ ፡ ወዐቀብከ ፡ ሕገ ፡ አራት፡ ቍልፈትከ ፡ ማዝረተ ፡ ትከውነከ ፡ ወትትፌጸም ፡ ላዕሌከ ፡ ቍልፈት ፡ ዘይፈጽማ ፡ በዓለ ፡ ሕግ ፡ እምጠባይዓቲሁ ።

፩ሺ፰፻፶፱ ወበእማን ፡ ኢይደሉ ፡ ተግዝሮ ፡ እምድኅረ ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትና ። ወዘይመርሕስ ፡ ላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ ፍጻሜ ፡ ቃሉ ፡ በእንተ ፡ ማዝረት ፡ ዘተናገረ ፡ ለሰብእ ፡ ቆሮንቶስ ፡ "ወይቤ ፡ የሀሉ ፡ ኵሉ ፡ ብእሲ ፡ እምኔክሙ ፡ በግብር ፡ ዘተጸውዐ ፡ ባቲ ፡ ኀበ ፡ ሃይማኖት" ። ወካዕበ ፡ እመሰ ፡ ኮነ ፡ ተግዝሮ ፡ ዘኢይደሉ ፡ ግሙራ ፡ እምኢያብሖ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ለጢሞቴዎስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ረድኡ ፡ በከመ ፡ ስምዐ ፡ ኮነ ፡ መጽሐፈ ፡ አብረክሲስ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ገዘሮ ።

ስለ ፡ ጠንቋዮና ፡ ስለ ፡ ማዝረት ፡

ነው ። ( ገላ ፡ ፭ ፡ ፮ ። ፲፭ - ፲፮ ) ።

፩ሺ፰፻፶፯ በአፍአ ፡ የምትገለጽ ፡ ትምህርቱ ፡ ግን ፡ ከማዝረት ፡ መከልከልን ፡ ትናገራለች ። ፈቃዱ ፡ መሠረቷ ፡ የማዝረት ፡ ትእዛዝ ፡ በሆነ ፡ በኦሪት ፡ ትእዛዝ ፡ ከመያዝ ፡ መከልከል ፡ ነበረና ። ኦሪትንም ፡ በጥንተ ፡ ስሟ ፡ ጠራት ። መጻሕፍት ፡ በጥንተ ፡ ስማቸው ፡ እንደተጠሩ ። እነርሱም ፡ ኦሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ ኦሪት ፡ ዘኍልቍ ፡ ናቸው ። በእንደዚህም ፡ ያለ ፡ መንገድ ፡ በተነገረው ፡ አንቀጽ ፡ የኦሪት ፡ ሕግ ፡ በማዝረት ፡ ስም ፡ ተጠራች ። ሁለተኛዋም ፡ ቍልፈት ፡ ተብላ ፡ ተጠራች ። በዚህም ፡ ላይ ፡ የሚያስረዳ ፡ ለቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ፡ በጻፈው ፡ በ፯ኛው ፡ ምስራፍ ፡ ሰው ፡ የተገዘረ ፡ ሆኖ ፡ ወደ ፡ ሃይማኖት ፡ ቢጠራ ፡ ወደ ፡ ቈላፍነት ፡ አይመለስ ። ያለው ፡ ቃል ፡ ነው ። (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፯ ፡ ፲፰ )።

፩ሺ፰፻፶፰ የዚህ ፡ ቃል ፡ አፍአዊ ፡ ንባቡ ፡ በማዝረት ፡ ሕግ ፡ ወደ ፡ ተነገረ ፡ መገዘር ፡ የሚያመለክት ፡ ከሆነ ፡ ይኸውም ፡ ሥጋን ፡ መቍረጥ ፡ ነው ። የተገዘረ ፡ ሰው ፡ ያልተገዘረ ፡ ወደመሆን ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ አይቻለውምና ፡ ወደ ፡ አለመገዘር ፡ አይመለስ ፡ ለምን ፡ አለ ? ይህንም ፡ ቃል ፡ ሰው ፡ ሆይ ፡ ብታምን ፡ ሕገ ፡ ኦሪትንም ፡ ካፈረስኸ ፡ ማዝረትህ ፡ ቍልፈት ፡ (አለመገዘር) ፡ ይሆንብሃል ፡ ብሎ ፡ ለሮም ፡ ሰዎች ፡ በጻፈው ፡ መልእክቱ ፡ ያስረዳል ። በቈላፍነት ፡ ሳለህ ፡ ሕገ ፡ ኦሪትን ፡ ብትጠብቅ ፡ ግን ፡ ቍልፈትህ ፡ (አለመገዘርህ) ፡ ማዝረትን ፡ ትሆንልሃለች ። በዓለ ፡ ሕግ ፡ ሰው ፡ ከባሕርዩ ፡ የሚፈጽማት ፡ ቍልፈትም ፡ ትፈጸምልሃለች ። (ሮሜ ፡ ፪ ፡ ፳፭ - ፳፱) ።

፩ሺ፰፻፶፱ ከክርስትና ፡ ጥምቀት ፡ በኋላ ፡ መገዘር ፡ በእውነቱ ፡ አይገባም ። በዚህም ፡ ላይ ፡ የሚያስረዳ ፡ ለቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ማዝረት ፡ የተናገረው ፡ የመጨረሻ ፡ ቃሉ ፡ ነው ። ከእናንተ ፡ ሰዉ ፡ ሁሉ ፡ ወደሃይማኖት ፡ በተጠራበት ፡ ግብር ፡ ጸንቶ ፡ ይኑር ፡ አለ ። (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፯ ፡ ፳) ። ዳግመኛም ፡ መገዘር ፡ ፈጽሞ ፡ የማይገባ ፡ ቢሆንስ ፡ ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ ለደቀ ፡ መዝሙሩ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ጢሞቴዎስ ፡ ባልፈቀደለትም ፡ ነበር ። (ባልገዘረውም ፡ ነበረ) ፡ የሐዋርያት ፡ ሥራ ፡ እርሱ ፡ እንደገዘረው ፡ ምስክር ፡ እንደ ፡ ሆነ ። (የሐዋ ፡ ፲፮ ፡ ፫ ።)

፩ሺ፰፻፲ ወለእመ ፡ ተብህለ ፡ እስመ ፡ ዕጸብ ፡ አገብሮ ፡ በእንተ ፡ ግዝረት ፡ ይከውን ፡ እውሥአትነ ፡ ከመ ፡ ግብር ፡ ሕጋዊት ፡ ትትከፈል ፡ ኀበ ፡ ፪ኤ ፡ ክፍል ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆ ፡ ፍትሕ ፡ ዘይደሉ ፡ ገቢሮቱ ፡ ወኢይደሉ ፡ ኀዲጎቱ ፡ በኵሉ ፡ ግብር ፡ ወበኵሉ ፡ ዘመን ፡ በእንተ ፡ ዘአበዘ ፡ ቦቱ ፡ ወአኀልአ ፡ እምኔሁ ። ወቦ ፡ ትእዛዝ ፡ ዘከመ ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡ እንተ ፡ ዘእንበሌሁ ፡ ኢይትረከብ ፡ መንግሥተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዘከመ ፡ ተዋሕዶት ፡ እምላካዊት ፡ ወትሥልስተ ፡ አካላቲሁ ። በከመ ፡ ይቤ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ "መልአክ ፡ እምሰማይ ፡ አው ፡ ካልእ ፡ እመ ፡ መሀረክሙ ፡ ካልአ ፡ እምዘመሀርናክሙ ፡ ንሕነ ፡ ውጉዘ ፡ ለይኩን" ። ወተማግጸሰ ፡ በእንተ ፡ ቀቲል ፡ ወዝሙት ፡ ይቤ ፡ ከመ ፡ እለ ፡ ይገብሩ ፡ እሎንተ ፡ ዐቢያተ ፡ ኢይወርስዋ ፡ ለመንግሥተ ፡ እግዚአብሔር ።

፩ሺ፰፻፲፩ ወዳግምኒ ፡ ዘይደሉ ፡ ገቢሮቱ ፡ ወኀዲጎቱ ፡ ዘከመ ፡ ጸሎት ፡ ወጾም ፡ ዘወትር ፡ ወተገዝሮ ፡ ዘሰምዐ ፡ ኮንዎ ፡ ከመ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ በ፪ኤ ፡ ፍናዌ ፡ በከመ ፡ አቅደምነ ፡ ዘከሮ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ኪያሁ ፡ እምግብራት ፡ ዘልማድ ። ወለኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ ዘለምሙ ፡ ምግባራት ፡ ዘልማድ ፡ ዘትጎኒ ፡ በኀቤሆሙ ። ወቦ ፡ ዘትከውን ፡ ኅሣረ ፡ በኀበ ፡ ካልአኒሃ ፡ ከመ ፡ ቀሪጸ ፡ ገጽ ፡ በኀበ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ወኖባ ፡ ወከመ ፡ ተላጽዮ ፡ ጽሕም ፡ በኀበ ፡ አፍርንጅ ፡ ወከመ ፡ ካህናት ፡ ሮም ፡ እለ ፡ ይላጽዩ ፡ ማእከለ ፡ አርእስቲሆሙ ። ወእሙንቱ ፡ ይብሉ ፡ እሉ ፡ ፪ቱ ፡ መዓርጋት ፡ ከመ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳቲሆሙ ፡ እዘዝዎሙ ፡ በዝንቱ ፡ ንብሎሙ ፡ ወከማሁ ፡ ቅብጣውያንኒ ፡ እለ ፡ ይትገዘሩ ፡ አብሕዎሙ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳቲሆሙ ፡ ከመ ፡ ይትገዘሩ ።

፩ሺ፰፻፲፪ ወቦ ፡ ዘይቤ ፡ ዘከመ ፡ ገብረ ፡ ሐዋርያ ፡ ግዝረተ ፡ በእንተ ፡ መፍቅድ ፡ ወበቍዔት ፡ ከማሁ ፡ ገብሩ ፡ ቅብጣውያን ፡ በእንተ ፡ መፍቅድ ፡ ወበቍዔት ። ወመፍቅድሰ ፡ በእንተ ፡ ዘኮኑ ፡ ኀዱራነ ፡ ማእከለ ፡ ግዙራን ፡ ወፍሡሕ ፡ ጸኑ ፡ ወሬዘቶሙ ፡ ኀበ ፡ ምግባራት ፡ እኩያት ፡ እስከ ፡ ይትገዘሩ ፡ እምድኅረ ፡ ነሢአ ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡ ወእምነ ፡ ዝንቱ ፡ ይትዐቀቡ ። ወካል

፩ሺ፰፻፲ ጭንቅ ፡ ነገር ፡ አስገድዶት ፡ ነው ፡ እኮ ፡ ቢባልም ፡ መልሳችን ፡ በሕግ ፡ የምትሠራ ፡ ሥራ ፡ ከሁለት ፡ እንደምትከፈል ፡ ይሆናል ። ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ ሊያደርጉት ፡ የሚገባ ፡ በሥራውም ሁሉ ፡ በዘመኑም ፡ ሁሉ ፡ ሊተውት ፡ የማይገባ ፡ ፍርድ ፡ ነው ። እርሱን ፡ ስለአዘዘ ፡ ከእርሱም ፡ ስለ ፡ አልከለከለ ፡ ሌላ ፡ ትእዛዝም ፡ አለ ። ይኸውም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ያለ ፡ እርሱ ፡ የማይገኝ ፡ እንደ ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡ እንደ ፡ አምላካዊት ፡ ተዋሕዶ ፡ እንደ ፡ አካላትም ፡ ሦስትነት ፡ ያለ ፡ ነው ። ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ መልአክ ፡ ከሰማይ ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ እኛ ፡ ካስተማርናችሁ ፡ ሌላ ፡ ያስተማራችሁ ፡ ቢኖር፡ የተለየ ፡ ይሁን ፡ እንዳለ ። (ገላ ፡ ፩ ፡ ፰) ። ስለ መግደልና ፡ ስለ ፡ ዝሙት ፡ ቅጣት ፡ ግን ፡ እሊህን ፡ ታላላቅ ፡ ኃጢአት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ አይወርሱዋትም ፡ አለ ። (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፱ - ፲፩) ።

፩ሺ፰፻፲፩ ሁለተኛውም ፡ ሊሠሩትና ፡ ሊተዉት ፡ የሚገባ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ ዘወትር ፡ ጸሎትና ፡ ጾም ፡ ያለ ፡ ነው ። አስቀድመን ፡ እንደተናገርን ፡ በሁለት ፡ ወገን ፡ የመሰከሩለት ፡ ግዝረትና ፡ ከልማድ ፡ ሥራዎች ፡ ወገን ፡ እርሱንም ፡ የሚመስለው ፡ ነው ። ለአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ የምትሻ ፡ የልማድ ፡ ሥራዎች ፡ አሏቸው ። በሌሎች ፡ ዘንድ ፡ ተዋርዶ ፡ የምትሆን ፡ ሥራም ፡ አለች ። በኢትዮጵያና ፡ በኖባ ፡ ዘንድ ፡ ፊትን ፡ እንደመተፍተፍ ፡ በአፍርንጅም ዘንድ ፡ ጽሕምን ፡ እንደመላጨት ፡ እንደ ፡ ሮም ካህናትም ፡ መሃል ፡ ራሳቸውን ፡ እንደሚላጩት ፡ ያለ ፡ ነው ። እሊህ ፡ ሁለቱ ፡ መዓርጋትስ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳቶቻቸው ፡ ይህን ፡ አዝዘዋቸው ፡ ነው ፡ ቢሉ ፡ የሚገዘሩ ፡ ግብጾችም ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳቶቻቸው ፡ እንዲገዘሩ ፡ አዝዘዋቸው ፡ ነው ፡ እንላቸዋለን ።

፩ሺ፰፻፲፪ ሐዋርያ ፡ ግዝረትን ፡ ስለፈቃድና ፡ ስለጥቅም ፡ እንደ ፡ አደረገው ፡ ግብጻውያንም ፡ ስለ ፡ ፈቃድና ፡ ስለጥቅም ፡ አደረጉት ፡ የሚል ፡ አለ ። መፍቅድስ ፡ በግዙራን ፡ መካከል ፡ የሚኖሩ ፡ ስለሆኑና ፡ ጎልማሶቻቸውም ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትናን ፡ ከመቀበል ፡ በኋላ ፡ እስኪገዘሩ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ እነሆ ፡ ስለአዘነበሉ ፡ ነው ። ከዚህ ፡ ግን ፡ ይጠበቁ ። እነሆ ፡

እት ፡ መፍቅዳት ፡ ዘናሁ ፡ ዘክርዎን ፡ በካልእ ፡ እምዝንቱ ፡ መጽሐፍ ።

፩ሺ፰፻፲፫ ወበእንተ ፡ በቀኖናትስ ፡ ናሁ ፡ ዘከረ ፡ ፩ዱ ፡ ጠቢብ ፡ እምፈላስፋ ፡ እለ ፡ የአምሩ ፡ ጥበበ ፡ ዘበበዓዱ ፡ ወይቤ ፡ እስመ ፡ በተግዘር ፡ ይደክም ፡ ኃዋየ ፡ ፍትወት ፡ ወየሐጽጽ ። ወዝንቱኒ ፡ በተሰናስዎ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ በዛቲ ፡ ሥርዓት ፡ ቅድስት ።

፩ሺ፰፻፲፬ ወተአምኖ ፡ ኃጣውእስ ፡ ፈውስ ፡ መንፈሳዊ ፡ ውእቱ ፡ ወተስምዮቱኒ ፡ በመንፈስ ፡ ዘያስተዛምድ ፡ ምስለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በከመ ፡ ተዘምዶ ፡ ሥጋዊ ፡ ያስተሳትፍ ፡ ምስለ ፡ ሥጋ ። ወበከመ ፡ ፈውስ ፡ ሥጋዊ ፡ ኢይትፌጸም ፡ ዘእንበለ ፡ በእደ ፡ ዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ ጠቢብ ፡ ወኄር ፡ ወእመ ፡ እኩስ ፡ ኀዲገ ፡ ተፈውሶ ፡ ይኄይስ ፡ እምተፈውሶ ፡ በእደ ፡ ዐበድ ፡ ወእኩይ ። ወዓዲ ፡ በተወክፎቱ ፡ ድዉይ ፡ ዘይትዐበር ፡ ሎቱ ፡ ዘይማንዮ ፡ እምዘይቤሎ ። ወካዕበ ፡ በዘይትከሀሎ ፡ ፈውሶት ፡ በከዊነ ፡ ዘመነ ፡ ወመካነ ፡ ወክሂል ፡ ወእመ ፡ እኩስ ፡ አልቦቱ ፡ በቀኖናት ፡ ወከማሁ ፡ መንፈሳዊኒ ።

፩ሺ፰፻፲፭ ወእምከመ ፡ ኢተረክበ ፡ ማእምረ ፡ ፈውስ ፡ ኢትመጽእ ፡ ሠናይት ፡ ወከማሁ ፡ በዝቱ ፡ ክፍል ከነ ፡ ተአምኖ ፡ ኃጣውእ ፡ ዘይትፈቀድ ፡ ኢይትረከብ ፡ ውስተ ፡ ገጽ ፡ ዘእንበለ ፡ በንስቲት ። ወቦ ፡ እምሊቃነ ፡ ጳጳሳቲሆሙ ፡ እለ ፡ ከልእ ፡ ኪያሁ ፡ በዓለም ፡ በእንተ ፡ ተኃጥኦተ ፡ እንብሮቶሙ ፡ ስዩቱ ፡ ውሳኔያት ፡ ዘኢይትፌጸም ፡ በሠናይ ፡ ዘእንበለ ፡ ባቲ ። ወበከመ ፡ ኢኮኑ ፡ ኵሎሙ ፡ ሰብእ ፡ ፈቃድያን ፡ ዘይፈቅዱ ፡ ኀበ ፡ ፈውስ ፡ ሥጋዊ ፡ ወከማሁ ፡ እንከ ፡ መንፈሳዊኒ ወበከመ ፡ ኢኮኑ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይፈቅዱ ፡ ኪያሁ ፡ ይፍቅድዎ ፡ ዘልፈ ፡ በኵሉ ፡ ደዌ ፡ ወከማሁ ፡ መንፈሳዊኒ ፡ ካዕበ ።

፩ሺ፰፻፲፮ ወዘሰ ፡ ብዙሕ ፡ ስሊቅ ፡ ዘውእቱ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ከመ ፡ ይሙስኩ ፡ ዲቤሁ ፡ ወያንትጉሣ ፡ እምኔሁ ፡ ዝኒ ፡ በአምሳለ ፡ ዘይሬእዩ ፡ ዘይከውን ፡ በቀኖናት ፡ በዘመኑ ። ወእእምር ፡ ከመ ፡ መፍቅደ ፡ ሕግ ፡ ይትከፈል ፡ ኀበ ፡ ፪ቱ ፡ አክፋል ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ አሚን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ ወካልእኒ ፡ ግብር ፡ ዘያሠምሮ ፡



ከዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ በሌላ ፡ የተናገሯቸው ፡ ሌሎች ፡ መፍቅዳትም ፡ አሉ ።

፩ሺ፰፻፲፫ ስለጥቅምስ ፡ ጥቡብን ፡ በየወገኑ ፡ ከሚያውቁ ከፈላስፎች ፡ አንዱ ፡ ፈላስፋ ፡ በመገዘር ፡ የፍትወት ፡ ዓባለ ፡ ዘርዕ ፡ ይደክማል ፡ ይቀንሳልም ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ። ይህም ፡ በስምምነት ፡ ከሆነ ፡ በዚች ፡ ቅድስት ፡ ሥርዓት ፡ የተገባ ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፲፬ ኃጢአትን ፡ መታመን ፡ መንፈሳዊ ፡ ፈውስ ፡ ነው ። በመንፈስ ፡ መባሉም ፡ ሥጋዊ ፡ ተዘምዶ ፡ ከሥጋ ፡ ጋር ፡ እንደሚያዛምድ ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጋራ ፡ ስለሚያዛምድ ፡ ነው ። ሥጋዊ ፡ ፈውስ ፡ ብልህ ፡ ቸር ፡ በሆነ ፡ በሐኪም ፡ እጅ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ እንደማይፈጸም ፡ ያለዚያስ ፡ ሰነፍ ፡ ክፉ ፡ በሆነ ፡ ሐኪም ፡ እድናለሁ ፡ ከማለት ፡ መድኃኒት ፡ ማድረጉን ፡ መተው ፡ ይሻላል ። ዳግመኛም ፡ መድኃኒት ፡ የሚያደርጉለት ፡ ድውይ ፡ ይበጅሃል ፡ ከአሉት ፡ ወገን ፡ የሚበጀውን ፡ በመቀበሉ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ እንደዘመኑ ፡ እንደቦታው ፡ እንደችሎታው ፡ ሁናቴ ፡ በሚቻለው ፡ መድኃኒት ፡ ነው ፡ እንዲህ ፡ ካልሆነስ ፡ ጥቅም ፡ የለውም ፡ መንፈሳዊውም ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፲፭ መድኃኒት ፡ በዋቂ ፡ ካልተገኘ ፡ ጤንነት ፡ አትመጣም ፡ (አትገኝም) ። እንደዚሁም ፡ የሚሻ ፡ ኃጢአትን ፡ መታመን ፡ በሁለት ፡ ክፍል ፡ ሆነ ፡ በአንዳንድ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በማናቸውም ፡ ዘንድ ፡ አይገኝም ። ከሊቃነ ፡ ጳጳሳቶቻቸው ፡ ወገን ፡ እርሱን ፡ የከለከሉ ፡ በዓለም ፡ አሉ ። በእርሱዋ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ በመልካም ፡ የማይፈጸም ፡ ፍቱን ፡ ውሳኔዎች ፡ እንድ ማድረግ ፡ ስለታጣ ፡ ነው ። ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ሥጋዊ ፡ ፈውስን ፡ የሚሹ ፡ ፈቃደኞች ፡ እንዳልሆኑ ፡ መንፈሳዊውም ፡ ደግሞ ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፲፮ ለሊቅ ፡ የሚገባውም ፡ ይኸውም ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ነው ፡ በዚህ ፡ ላይ ፡ ሊጠብቅም ፡ ከዚህም ፡ ሊያጎድል ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በዘመኑ ፡ የትም ፡ የሚሆነውን ፡ በማየቱ ፡ ልክ ነው ። የሕግ ፡ ፈቃድ ፡ ከሁለት ፡ ክፍል ፡ እንደሚከፈል ፡ ዕወቅ ፡ ከእነዚህም ፡ አንዱ ፡ በልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ማመን ፡ ሁለተኛውም ፡ ደስ ፡ የሚያሰ

አንቀጽ ፡ ፶፩ ።

፩ሺ፰፻፲፯ ወቀዳማዊኒ ፡ ዘውእቱ ፡ ክፍል ፡ ዘውእቱ ፡ ጽሒፍ ወውእቱ ፡ ጽሒፈ ፡ ቃል ፡ ወትርጓሜሁ ። ወለዘተጽሕፈስ ፡ ኢይከውኖ ፡ ለመኑሂ ፡ ከመ ፡ ይወስክ ፡ ዲቤሁ ፡ ወኢከመ ፡ ያንትግ ፡ እምኔሁ ፡ በእንተ ፡ ቃለ ፡ ሐዋርያ ፡ ዘይቤ ፡ "መልአክ ፡ እምሰማይ ፡ ለእመ ፡ መሀረክሙ ፡ ካልአ ፡ እምዘመሀርናክሙ ፡ ንሕነ ፡ ውጉዘ ፡ ለይኩን" ። ወትርጓሜሁስ ፡ ኢይከውኖ ፡ ለመኑሂ ፡ ከመ ፡ ይፈክር ፡ ውስቴቱ ፡ ዘይትቃወሞ ፡ ለዘተጽሕፈ ፡ ወኢበዘተጋብኡ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወኢ ፡ ላዕለ ፡ ዘተጽሕፈ ፡ በምክሮሙ ፡ ለብዙኃን ፡ እመተርጉማን ፡ ማእምራን ፡ ወቅዱሳን ።

፩ሺ፰፻፲፰ ወዳግምኒ ፡ ኀበ ፡ ዘውእቱ ፡ ክፍል ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘለዉቅ ፡ ውስተ ፡ ዘተጽሕፈ ፡ ዘውእቱ ፡ ቃለ ፡ መጻሕፍት ፡ እምላካውያት ፡ ወጉባኤያት ፡ ውኩፋት ፡ ዘከመ ፡ ጾም ፡ ወጸሎት ፡ ወምጽዋት ፡ ወዘይመስሉ ፡ ለዝንቱ ። ወዝንቱኒ ፡ ይከውን ፡ ከመ ፡ ቀዳማዊ ፡ በዘይትገበር ፡ ቦቱ ፡ ኪያሁ ። ወካልእኒ ፡ ዘኢተማህደ ፡ በመጻሕፍት ፡ እንተ ፡ እመርን ፡ ኀቤሃ ፡ ወኢኮነ ፡ ከሠተ ፡ ይግበሩ ፡ ባቲ ፡ ወኢተረክበ ፡ ጉባኤ ፡ በእንቲአሃ ፡ አላ ፡ ውእቱስ ፡ እምግብር ፡ እንተ ፡ ኢዘከርዋ ።

፩ሺ፰፻፲፱ ወለዝንቱ ፡ ባሕቲቱ ፡ ቦቱ ፡ መባሕት ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ወይእስር ፡ ወባሕቱ ፡ ይግበር ፡ በሥርዓተ ፡ ውሳኔ ። ቀዳሚሃኒ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ፍጹመ ፡ ልቡና ፡ በአእምሮ ፡ ጠባይዓዊ ፡ ወረባኃዊ ።

፩ሺ፰፻፳ ወዳግምኒ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ጽኑዕ ፡ በሃይማኖቱ ፡ ዘየዐቅብ ፡ ቦቱ ፡ ሕገ ፡ ሃይማኖት ፡ ዘሀሎ ፡ ዲበ ፡ መሠረታቲሁ ፡ ዘዘለፍ ።

፩ሺ፰፻፳፩ ወሣልስ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ምሁረ ፡ በ፪ቱ ፡ እሥራው ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ቃለ ፡ መጻሕፍት ፡ እምላካውያት ፡ ወትርጓሜሆን ፡ ዘዮን ብር ፡ ቦቱ ፡ ወዳግም ፡ ሀተጋብኡ ፡ ወነብሩ ፡ ላዕሌሁ ፡ ማኅበረ ፡ ቅዱሳን ፡ ማእምራን ፡ ወዘነብሩ ፡ ላዕሌሁ ፡ ካዕበ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ስንእዋን ፡ ላዕለ ፡ ዘነብሩ ፡ ቦቱ ። ወይለብዎ ፡ በጥዩቅ ፡ ለዘተናፈቁ ፡ በእንቲአሁ ፡ ወይትአመንዎ ፡ ለዘተሰነአዉ ፡ ላዕሌሁ ።

ስለ ፡ ጠንቋይና ፡ ስለ ፡ ሟርት ።

ኛውን ፡ ሥራ ፡ መሥራት ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፲፯ መጀመሪያው ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ነው ። ይኸውም ፡ መጻፍ ፡ ነው ። እርሱም ፡ ንባቡንና ፡ ትርጓሜውን ፡ መጻፍ ፡ ነው ። የተጻፈውን ፡ ማን ፡ ስማንም ፡ ቢሆን ፡ በእርሱ ፡ ሊጨምር ፡ ከእርሱም ፡ ሊያጎድል ፡ አይገባውም ። ሐዋርያ ፡ እኛ ፡ ካስተማርናችሁ ፡ ሌላ ፡ መልአክ ፡ ከሰማይ ፡ ቢያስተምራችሁ ፡ የተለየ ፡ ይሁን ፡ ስለ አለ ፡ ነው ። ትርጓሜውም ፡ የተጻፈውን ፡ ወይም ፡ የተባበሩትን ፡ ቅዱሳን ፡ ሊቃውንት ፡ ከሚሆኑ ፡ ከመተርጉማን ፡ ወገን ፡ በብዙዎች ፡ ምክር ፡ የተጻፈውንም ፡ የሚቃወም ፡ አድርጎ ፡ ይተረጉም ፡ ዘንድ ፡ ለማንም ፡ አይገባውም ።

፩ሺ፰፻፲፰ ሁለተኛውም ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ነው ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ በተጻፈው ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ የቅዱሳት ፡ መጻሕፍትና ፡ ተቀባይነት ፡ ያላቸው ፡ የጉባኤያት ፡ ቃል ፡ ነው ። ይኸውም ፡ እንደ ጾምና ፡ እንደ ጸሎት ፡ እንደ ምጽዋትም ፡ ይህንም ፡ እንደመሰለ ፡ ያለ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በሚሠራበት ፡ ነገር ፡ እንደ ፊተኛው ፡ ይሆናል ። ሁለተኛውም ፡ በጠቀስነው ፡ መጽሐፍ ፡ ያልተነገረ ፡ ይሠሩበትም ፡ ዘንድ ፡ ግልጥ ፡ ያልሆነ ፡ ነው ። ስለእርሱዋም ፡ ጉባኤ ፡ አልተደረገም ። ከአልጠቀስዋት ፡ ሥራ ፡ ወገን ፡ ነው ፡ እንጂ ።

፩ሺ፰፻፲፱ በዚህ ፡ ብቻ ፡ ሊፈታ ፡ ሊያስር ፡ ሥልጣን ፡ አለው ። ነገር ፡ ግን ፡ በውሳኔ ፡ ደንብ ፡ ያድርግ ፡ መጀመሪያዋም ፡ በጠባይዐዊና ፡ በጠቃሚ ፡ አእምሮ ፡ ፍጹም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፳ ሁለተኛው ፡ በዘለዓለም ፡ መሠረቶቹ ፡ የአለ ፡ የሃይማኖቱን ፡ ሕግ ፡ በሚጠብቅበት ፡ በሃይማኖቱ ፡ የጠራ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፳፩ ሦስተኛ ፡ በሁለቱ ፡ መሠረቶቹ ፡ የተማረ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ የቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ፡ ቃልና ፡ የሚተባበር ፡ ትርጓሜያቸው ፡ ነው ። ሁለተኛም ፡ ቅዱሳን ፡ ሊቃውንት ፡ የሆኑ ፡ የተባበሩበትና ፡ አንድ ፡ የሆኑበት ፡ ዳግመኛም ፡ በተባበሩበት ፡ ላይ ፡ የተስማሙ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ የተባበሩበት ፡ ነው ። ስለእርሱም ፡ የተለያዩበትን ፡ በጥንቃቄ ፡ ያስተውሉት ፡ የተስማሙበትንም ፡ ይመኑበት ።

እንቀጽ ፡ ፺፩ ።

፩ሺ.፰፻፺፩ ማልስ ፡ እእምሮተ ፡ እምሳል ፡ ዘያበጽሕ ፡ ኀበ ፡ እማብእተ ፡ እዕፁቅ ፡ ዘንበር ፡ ላዕሌሃ ፡ ኀበ ፡ ሥርወ ፡ ጕንድ ፡ ዘትትበሃል ፡ ባቲ ፡ ኀበ ፡ ትርጓሜያት ፡ ወጉባኤያት ፡ እንተ ፡ ተሰነአዉ ፡ ባቲ ።

፩ሺ.፰፻፺፪ ወራብዕሰ ፡ ትእዛዝ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ማእምረ ፡ በገሃድ ፡ ወልማድ ፡ እምግብራት ።

፩ሺ.፰፻፺፫ ወኃምስ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ትሩፈ ፡ ምግባር ፡ በውስተ ፡ ነፍሱ ፡ ወሥጋሁ ፡ በዘይከውን ፡ ውኩፈ ፡ ትእዛዘ ፡ ዚአሁ ፡ በኀበ ፡ ሕዝብ ።

፩ሺ.፰፻፺፬ ሳድስ ፡ ከመ ፡ ይርአይ ፡ ዘይሠርዕ ፡ ሎሙ ፡ ዘይትከሀሎሙ ፡ ፀዊሮቱ ፡ በመዋዕሊሁ ፡ ወለዘ ይከውኑ ፡ እሙንቱ ፡ ነዳያነ ፡ ላዕሌሁ ፡ እምሳለ ፡ ዘይረብሖሙ ፡ ትምህርተ ፡ ለባዊተ ፡ ዘይጠናቀቁ ፡ ባቲ ፡ ሐልዮታቲሆሙ ፡ ወቀንዮተ ፡ ፈቃዳቲሆሙ ፡ ዘትሜኒ ፡ ባቲ ፡ ገድሎሙ ፡ ወትትፌጸም ፡ ባቲ ፡ እምልኮቶሙ ፡ ወእንተ ፡ ትደሉ ፡ ለሠናይቶሙ ፡ ወግብረ ፡ ሥርዓቶሙ ፡ ዘትትፌጸም ፡ ባቲ ፡ ሃይማኖቶሙ ፡ ጥዩቀ ፡ ወዘ ይረትዕ ፡ ባቲ ፡ ግብሮሙ ፡ በዓለሞሙኒ ፡ ወደኃሪቶሙኒ ።

፩ሺ.፰፻፺፭ ወሳብዕ ፡ ከመ ፡ ይትማከር ፡ በዘይፈትሕ ፡ ወየአስር ፡ ምስለ ፡ ማእምራን ፡ ወንጹሓን ፡ እም ካህናቲሁ ፡ ወሕዝቡ ፡ ወመኳንንቲሁ ፡ ወቅሩ ባኒሁ ፡ ዘታሕተ ፡ ሥልጣኑ ፡ በባሕቲቶሙ ፡ ወበተጋብኦ ፡ ወእምድኅረ ፡ ተሰነአዉ ፡ ቦቱ ፡ ይጽሐፉ ፡ ተዘካረ ፡ ነገር ፡ ምክንያቱ ፡ ዘተጋ ብኡ ፡ በእንቲአሁ ፡ ወተመክንዮተ ፡ በቀኖናት ፡ ዘቦቱ ፡ ወከዊኖ ፡ ተሰናእዎ ፡ ዘካህናት ፡ ወመኳ ንንት ፡ ዘላዕሌሁ ። ወለእመኒ ፡ ኮነ ፡ ግብረ ፡ ዐቢየ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይትጋብኡ ፡ በእንቲአሁ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ወዐበይተ ፡ ካህናት ፡ ወመኳ ንንት ፡ ወዘቦቱ ፡ እእምሮ ፡ ወገቢረ ፡ ጽድቅ ። ወይጽሐፉ ፡ ጽሕፈተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ላዕለ ፡ ዘተ ጽሕፈ ፡ ወያሰልጡ ፡ እምኔሁ ፡ መጻሕፍተ ፡ ወያንብብዎሙ ፡ ውስተ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያ ናት ፡ ቅድመ ፡ ካህናት ፡ ቅድመ ፡ ኵሉ ፡ ውስተ ፡ ብሔር ፡ ወአህጉር ።

፩ሺ.፰፻፺፮ ክፍል ፡ በእንተ ፡ ዘይደሉ ፡ ተእኀዞ ፡ ምስለ ፡

ስለ ፡ ጠጕርና ፡ ስለ ፡ ማኅበረት ።

፩ሺ.፰፻፺፩ ሦስተኛውም ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ያሉ ፡ ቅርን ጫፎችን ፡ በትርጓሜና ፡ በተሰማሙበት ፡ ጉባኤ ፡ ወደምትነገር ፡ ወደማንደ ፡ ሥር ፡ ወደ መመለስ ፡ የሚያደርስ ፡ ምሳሌን ፡ ማወቅ ፡ ነው ።

፩ሺ.፰፻፺፪ ዐራተኛውም ፡ ትእዛዝ ፡ ከሥራዎች ፡ ወገን ፡ በግልጽና ፡ በልማድ ፡ ዐዋቂ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፩ሺ.፰፻፺፫ አምስተኛው ፡ በሕዝብ ፡ ዘንድ ፡ ተቀባይ ፡ በሚሆን ፡ ትንዛዙ ፡ በነፍስና ፡ በሥጋዉ ፡ በሥራ ፡ ፍጹም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፩ሺ.፰፻፺፬ ፮ኛ ፡ በዘመኑ ፡ የሚሠራላቸው ፡ ሥርዓት ፡ መሸከሙ ፡ የሚቻላቸው ፡ እንደሆነ ፡ ወይም ፡ እነርሱ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ችግረኞች ፡ የሚሆኑ ፡ (የማይችሉት) ፡ እንደሆነ ፡ ይመለከት ፡ ዘንድ ፡ ነው ። አሳቦቻቸው ፡ የሚታረሙበት ፡ ፈቃዶ ቻቸው ፡ የሚገዙበት ፡ ገድላቸው ፡ የምትበጅ ባት ፡ አምልኮታቸው ፡ የምትፈጸምበት ፡ ለመ ልካምነታቸውና ፡ ለሥርዓታቸው ፡ ማብር ፡ የም ትገባ ፡ ሃይማኖታቸው ፡ በእርግጥ ፡ ፍጹም ፡ የምትሆንበት ፡ በዓለማቸውና ፡ በመጨረሻቸ ውም ፡ (በኋላኛው) ፡ ሥራቸው ፡ የምትቀናበት፡ ልባዊት ፡ ትምህርትን ፡ እንደሚጠቅማቸው ፡ ነው ።

፩ሺ.፰፻፺፭ ሰባተኛም ፡ ስለሚፈታውና ፡ ስለሚያስ ረው ፡ ከካህናቱ ፡ ወገን ፡ ከዐዋቆችና ፡ ከንጹ ሖን ፡ ከሕዝቡ ፡ ከመኳንንቱ ፡ ከሥልጣኑ ፡ በታች ፡ ከአሉ ፡ ከባለሟሎቹም ፡ ጋር ፡ በየብቻ ቸው ፡ በስብሰባም ፡ ይማከር ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ከተሰማሙበት ፡ በኋላ ፡ ስለእርሱ ፡ የተሰበሰቡ በትን ፡ የነገሩን ፡ ማስታወሻ ፡ በእርሱ ፡ የሚገ ኘውን ፡ የጥቅሙን ፡ ምክንያት ፡ በእርሱም ፡ ላይ ፡ የካህናቱና ፡ የመኳንንቱን ፡ የስምምነት ፡ ሁኔታ ፡ ይጻፉ ። ነገሩ ፡ ታላቅ ፡ ቢሆን ፡ ስለእ ርሱ ፡ ኤጲስቆጶሳትና ፡ ከካህናት ፡ አለቆች ፡ መኳንንትም ፡ እውቀትና ፡ የእውነት ፡ ሥራ ፡ ያለውም ፡ ሊሰበሰቡ ፡ ይገባል ። በተጻፈውም ፡ ላይ ፡ በእጃቸው ፡ ፊርማ ፡ ያፈርሙ ። (በእጃ ቸው ፡ ጽሕፈት ፡ ይጻፉ) ፡ ከእርሱም ፡ ደብዳቤ ዎችን ፡ ገልብጠው ፡ በካህናቱና ፡ በሁሉ ፊት ፡ በገጠርና ፡ በከተሞች ፡ በየቤተ ፡ ክርስቲ ያኑ ፡ ያንብቡአቸው ።

፩ሺ.፰፻፺፮ ክፍል ። ፍጹሜዋ ፡ ከኒቅያ ፡ ጉባኤ ፡ ጋር ፡

ቀኖና ፡ ኒቅያ ፡ ተፍጻሜታ ፡ ወይትኀሠሥ ፡ ዝንቱ ፡ ውስተ ፡ መጻሕፍተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወይጠይቅ ፡ እምሐራ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እስመ ፡ የእምር ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ እዘዘ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእንተዝ ፡ ኵሉ ። ወለእመሰ ፡ ተዐደወ ፡ ፩ዱ ፡ ዘእቅደምነ ፡ ነጊሮቶ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ተቃወሞ ፡ ለእግዚአብሔር ።

፩ሺ፰፻፹፰ ወይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ "ዘሰ ፡ ኮነ ፡ እምእግዚአብሔር ፡ ውእቱ ፡ ይሰምዕ ፡ ነገረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዓዲ ፡ ይቤ ፡ ብፁዕ ፡ ውእቱ ፡ ዘይሰምዕ ፡ ነገረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወየዐቅቦ ። ወይቤ ፡ ለአርዳኢሁ ፡ ዘሰምዐ ፡ እምኔክሙ ፡ ኪያየ ፡ ሰምዐ ፡ ወዘዐለወኒክሙ ፡ አበየኒ" ።

፩ሺ፰፻፹፱ ወይቤሉ ፡ ሐዋርያትኒ ፡ በውስተ ፡ ተፍጻሜተ ፡ ቀኖናት ፡ ዘንትሉ ፡ ዘወንጌሉ ፡ ንእዝዘክሙ ፡ ንሕነ ፡ ለ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ዘንተ ፡ ቀኖና ፡ ወለእመ ፡ ነበርክሙ ፡ ቦቱ ፡ ትትባልሑ ፡ ወትከውኑ ፡ ሰላም ፡ ለክሙ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ። ወለእመሰ ፡ ኢተወከፍክሙ ፡ ወኢተእዘዝክሙ ፡ ለዘውስቴቱ ፡ ይእዜ ፡ ትከውኑ ፡ ለስቃይ ፡ ወታኀብሩ ፡ ኀበ ፡ በበይናቲክሙ ፡ ወእምድኅረዝ ፡ ትነሥኡ ፡ ኵነኔ ፡ ዘይደሉ ፡ ለዕልወታቲክሙ ።

፩ሺ፰፻፺ ወእግዚአብሔር ፡ ባሕቲቱ ፡ ወወልዱ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ፈጣሬ ፡ ኵሉ ፡ ፍጥረታት ፡ ይረሲክሙ ፡ ፩ደ ፡ ሥጋ ፡ ለኵልክሙ ፡ በብዝኀ ፡ ሰላሙ ። ወያስተጋብኡ ፡ ለክሙ ፡ ኵሎ ፡ መፍቅደ ፡ ከመ ፡ ኢትትመየጡ ፡ ውስተ ፡ ዘእንበለ ፡ ደንብ ፡ ወዘእንበለ ፡ ኀጢአት ። ወይረሲክሙ ፡ ድልዋነ ፡ ለማኅደረ ፡ ሕይወት ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡ እመንገለ ፡ ወልዱ ፡ ፍቁር ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪ ፡ መድኀኒነ ፡ ዝንቱ ፡ ዘበእንቲአሁ ፡ ምስሌሁ ፡ ስብሐት ፡ ወምስለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡ ዓለም ፡ አሜን ።



መያያዝ ፡ ስለሚገባ ፡ ያናገራል ። ይህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ መጻሕፍት ፡ ይመርምር ። ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጭፍሮችም ፡ ይረዳ ። ስለዚህ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደአዘዘ ፡ ርሱ ፡ ያውቃልና ። አንድ ፡ ሰው ፡ አስቀድመን ፡ የተናገርነውን ፡ ቢደፋፈር ፡ ግን ፡ ርሱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተቃወመ ፡ እኮ ።

፩ሺ፰፻፹፰ ጌታችንም ፡ በወንጌል ፡ "ከእግዚአብሔር ፡ የሆነ ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ ይሰማል ፡ አለ ። (ዮሐ ፡ ፰ ፡ ፵፯) ። ዳግመኛም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ ሰምቶ ፡ የሚጠብቀው ፡ ብፁዕ ፡ ነው ፡ አለ ። (ሉቃ ፡ ፲፩ ፡ ፳፰) ። ለደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ እናንተን ፡ የሰማ ፡ እኔን ፡ ሰማ ፡ እናንተንም ፡ እንቢ ፡ ያለ ፡ እኔን ፡ እንቢ ፡ አለ ፡ አለ ። (ሉቃ ፡ ፲ ፡ ፲፮) ።

፩ሺ፰፻፹፱ ሐዋርያትም ፡ ቀጥርዋ ፡ ፶፯ ፡ በምትሆን ፡ በመጻፋቸው ፡ መጨረሻ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ ይህን ፡ ትእዛዝ ፡ እናዝዛችኋለን ። በእርሱም ፡ ብትኖሩ ፡ ትድናላችሁ ። እስከ ፡ መጨረሻም ፡ ድረስ ፡ ሰላም ፡ ለእናንተ ፡ ትሆናለች ፡ እሉ ። ባትቀበሉ ፡ ግን ፡ ዛሬም ፡ በውስጡ ፡ ሳላችሁበት ፡ ባትታዘዙ ፡ ለመዘባበቻ ፡ ትሆናላችሁ ። እርስ ፡ በእርሳችሁም ፡ ኅዘንን ፡ ታኖራላችሁ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ስወንጀለኛነታችሁ ፡ የሚገባ ፡ ቅጣትን ፡ ትቀበላላችሁ ።

፩ሺ፰፻፺ ብቸኛው ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጁ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ ፍጥረቶችን ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በሰላሙ ፡ ብዛት ፡ ሁላችሁን ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ያድርጋችሁ ። በኀውንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያዘጋጅላችሁ ። እንዳትመለሱ ፡ ያለ ፡ ነውርና ፡ ያለ ፡ ኀጢአት ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ። እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ ለሕይወት ፡ ማደሪያ ፡ የበቃችሁ ፡ ያድርጋችሁ ። እርሱ ፡ ፈጣሪ ፡ መድኀኒታችን ፡ እግዚአብሔር ፡ በልጁ ፡ በወዳጁ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በእርሱ ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ጋራ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይግባው ፡ አሜን ።

---

## አንቀጸ ተዋርሶ ።

ዘተሰነወ ፡ ላዕሌሁ ፡ እግዚእ ፡ አባ ፡ ቄርሎስ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘእለ ፡ እስክንድርያ ፡ ምስለ ፡ ኤጲስቆጶሳቲሁ ፡ ወሊቃውንቲሁ ፡ ወመኳንንቲሁ

## የመወራረስ አንቀጽ ።

የእስክንድርያ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ጌታ ፡ አባ ፡ ቄርሎስ ፡ ከኤጲስቆጶሳቱ ፡ ከሊቃውንቱና ፡ ከመኳንንቱ ፡ ጋራ ፡ የተስማሙበት ፡ ነው ።

